# ሀበሺ ኛ



ሀማ ቱማ

703-553-0567
Addisu

# ሀበሺ.ኛ

(የግጥም ስብስብ)

ሀማ ቱማ

ይህች የግጥም ስብስብ በመታሰቢያነት
ለእናቴ ለወ/ሮ እታፈራሁ ኀ/ማርያም
ተሰጥታለች

በ 1992 ዓ/ም (1999) ታተመ



የኢትዮጵያ ደራስያን ነጻ ማህበር

P.O. BOX 2465

WINNIPEG,MANITOBA

R3C 3R5 CANADA.

## ክፍል አንድ

## ከራስ ጋር ጨዋታ

### ሁሉ ተቀይሮ

ገና ስንወለድ
    ገና ጮጮ ሳለን
ያኔ በዚያን ጊዜ ለእኛ የተነገረን
መስረቅ መግደል ኃጢያት
            ከእግዜር የሚያጣላ
ዛሬ ግን መልዕክቱ ሁሉም ተቀይሮ
ግደለው ቅበረው
ዝረፍ አስለቅሰው
በዝብዝ አሰቃየው
የሚል ምክር ገኖ
ያደግንበት ሂደት በውዥንብር ተኖ
ከሀገር በላይ ነፍስ ሲባል የነበረው
ዛሬ ተቀይሮ
ክህደት-ዘውድ በራስ ላይ
ሁሉን መካድ ነግሶ
ያ የተነገረን ተጨራምቶ ወድቆ
ሀገር-ወገን ማለት መሳለቂያ ሆኖ
የዜጋ ማንነት ሰብዕና ሕይወት
ሆኖ ክህደት-ውርደት
ሞቶ አለና ማለት ተጨማልቆ ኑሮ
መበርከት መሰንበት ብልጥነት ተብሎ

ወግ-ታሪክ ተዋርዶ
ውርደት ካባ ሆኖ
በኩራት ተለብሶ
'ምታኮራን ሀገር ጩኸቷ ተረስቶ
ሰውነኝ በሚል ተባይ ታሪኳ ተበልቶ
ዳንኪራ ሬሳ ላይ
ሀገር ሁሉ ራቁት ተኘ በአደባባይ
ድሪቶ ውድ ሆኖ
ሁሉ ተደርቶ
ማንነት ራሱ የዘመናት ታሪክ
ተቀዶ ተጥሎ-መሳለቂያ ሆኖ
ያደግንበት ታሪክ ያ የተነገረን
ያ ያኮራን ታሪክ ባህል ወግ የሆነን
በመናኛ ሰዎች ሁሉ ተቀይሮ
መግደል መቅበር ወንጀል
የሚያስከብር ሆኖ
ይኸም ያም ተክዶ
ክህደት ውርደት ነግሶ
ሁሉ ተቀይሮ
ያ ኢትዮጵያዊነት
በመናኛ ሰዎች በእብሪት ተሰርዞ
ሁሉም ተቀይሮ
ዛሬም ለአረመኔ በባርነት አድሮ
በጠራራ ጸሐይ ምድራችን ጨልሞ
ሁሉ ተቀይሮ።

## ግዴታ

በእያንዳንዱ ደጃፍ አበባው ረግፎ
ሬሳው ተሰጥቶ
ከእያንዳንዱ ደጃፍ ጎመን ዱባ ጠፍቶ
የሕጻን ጭንቅላት ታጭዶ ተከምሮ
የእናት እንባ እንዳይፈስ ተከልክሎ ኖሮ





በልቧ ውስጥ ፈሶ
የበቀል ቁልቋልን አንጀቷ አብቅሎ
ሁሉ ቤት የለቅሶ
ሁሉ ቤትም ጋይቶ
የብዙሀኑም ዓይን በሀዘን ብዛት ጠፍቶ
የክላሺን ጥይት ሙጀሌን አስንቆ
ሁሉን አሽመድምዶ
በእያንዳንዱ ደጃፍ ሬሳው ተሰጥቶ
የሀገሪቷ ተስፋ በያለበት ደቆ
የለጋ ትውልድ ደም ነጋ-ጠባ ሳይል
ባገር ሁሉ ፈሶ
የወርቅ ዜጋ ሕልም ጭንቀት-ቅዠት ሆኖ
የሕዝብ ደም ፈሶ
ላባደሩ ደምቶ
አርሶአደሩ ደምቶ
ወጣት-ሽማግሌው
ምሁር ያልተማረው
ሁሉም ደምቶ ሞቶ
በሕዝብ ሬሳ ላይ ሥልጣን ተገንብቶ
የሚያረዳ ጠፍቶ ሁሉም ተረጂ ሆኖ
መለመን ፋይዳ ቢስ ሁሉ ለማኝ ሆኖ
ወርቅ ትውልድ ታግሎ
ታግሎ ደምቶ ሞቶ
ባፈፈሰሰውም ደም ባንዲራችን ቀልቶ
ትዝታችን ሁሉ በየተራ ደምቶ
እንባችን ራሱ ሲፈስ ሁሌ ቀልቶ
በሀዘን ብዛትም ልብ ያልነውም ተኖ
ማዘን ርህራሄ ማዘኛውም ጠፍቶ
ያ የፈሰሰው ደም በቀልን አምርቶ
ለመበቀል ጊዜ ጊዜ ራሱ ጠፍቶ
እንደገና መድማት
የሬሳ ምርት ማየት
ዕጣ ጣጣ ሆኖ
ቀሪው ትውልድ ሸሽቶ
ቀሪው ትውልድ ታግሎ

ዛሬም እንደትላንት ሀጻን ሳይቀር ደምቶ
በዱር በገደሉ ተኳሽ ሚቹ በዝቶ
በሕዝብ ራሳ ላይ ሥልጣን ተመስርቶ
ታሪክ የምንለው የግፍ ስርዓት ገድሉ
ቀጣይ ምጸት ሆኖ
ታሪክ በደም ቀልቶ
ያ ለጋ ትውልድም ለሁሉም የደማው
ከሥጋ ተላቆ አጥንቱ የቀረው
በተራ ከጉደንድ ተቆፍሮ ወጥቶ
ለንግድ-ፖሊቲካ ከግልጋሎት ውሎ
ገዳይ ዳኛ ሆኖ በሚቹ ላይ ሲያሾፍ
ባንዲራ ከጭቃ የሀገር ክብር ሲረግፍ
አበባው ሳያብብ ወዲያውን ሲቀጠፍ
በሀገር ሙሉ ራሳ
ዋይዋይታው ሲበዛ ሥቃይ ሲትረፈረፍ
የሰው ልጅ ግዴታ
የሰው ልጅ ሰውነት
ከእንስሳ መለየት
ማመጽ እምቢኝ ማለት፡፡

## በራሴ

ጭው ባለበት በረሐ
በለየለት ምድረበዳ
በሽምብራ ዛፍ ጥላ ስር ተቀምጬ
የሚያዋየኝ ሳገኝ ስጠብቅ
መሽቶ ነጋ ወር አለፈ
ዓመት ቆጠርኩ ተሰፋ ቆረጥኩ
ከእኔው ጋር ንትርክ
እንደገና ጀመርኩ ፡፡





## ነገ

ለዘመናት ጥሬ ግሬ
የደም ዋጋ ከፍዬ
ነገን በእጄ ሳስገባ
ትላንት ሆነብኝ
ከዛሬም ከፍቶ ገች አለብኝ፡፡
ትላንት ዛሬ ነገ
እኔው ራሴ ነኝ
ሲልም ቀለደብኝ፡፡
ትላንት ነገ ሆኖ
ዛሬን አደባይቶ
አልፎቶ አሾፈብኝ፡፡

## የቁም ሞት

በድን ሆኜ ሬሳ
ምን ቢረግጡት የማይነቃ
የማልነሳ
መብቴ የማልል ሀገሬ
የማልል ክብሬ
ሆኜ በድን ሬሳ ሆኜ
የሞቀኝ መቃብሬ
ሕይወት አለኝ ብዬ ተንሰፈሰፍኩ
የኖርኩኝ መስሎኝ ተፍረከረኩ
ሰንሰለቴን ዕድሜ ልክ ኀተትኩ
ሙት መሆኔን መች አወቅኩ፡፡

## ቅዠት

በጨለመ ዋሻ ገብቼ
በዝንጀሮ ሽንት በከረፋ
ጥቅጥቅ ካለ ጫካ ገብቼ
በፋና ደም በቀላ
ከሰማይ ጸሐይ ተጋርጄ
ድንገት ብርሀን ታየኝ ወገግ ብሎ
ተገለጠልኝ የከረመው ምስጢር ሆኖ
ዓይኔን ጨፍኜ ሁሉ ታየኝ
እንጉል ሕልሜ እውነት መሰለኝ።

## መች ሰርቶ?

ሰባት ቀን ቢሰራ
ለዘመናት አርፏል
ፈጠርኩ ካለ ኋላ
ዘለዓለም ተኝቷል
የእንባ ጎርፍ ብንሰድም
የማይነቃ ሆኗል
የማይሰማ ሆኗል።
እግዜር መቸ ሰርቶ
መቸ ጥሮ ግሮ
እኛን ስሩ ይላል
እኛን ልፉ ይላል?

## ነፍሴ

ሽፍቶች በመንገድ ከትረውኝ
ከገንዘብ ከነፍስህ ብለው ቢያስፈራሩኝ
ነፍሴን ሰጠኋቸው
ገንዝብ ነፍሴ እንደሆን ማን በነገራቸው።
አለገንዝብ ሕይወት
ከቶም እንደሌለኝ





ማንስ ባዋያቸው።
ገንዝቤን አድኜ
ነፍሴን ሰጠኋቸው
የሞተን ቢወስዱ ምኑ ሊጠቅማቸው?

## ለመኖር

ሕይወትን ለመኖር
መኖርን ለመኖር
ሞትን መድፈር ያሻል
ሞትን ሚጋፈጥ ሰው
ሕይወቱን ይወዳል
ገዳይን ይጠላል።
የሕይወት ትርጉሙ
ሞትን መፍራት ሳይሆን
ደፍሮ ወግድ ማለት
መሆኑንም አውቋል።
ሞትን የፈራ ሰው በቁሙ ይሞታል።

## እግዜር አፈረብን

በመከራ ሐሩር
በሥቃይ ዶፍ ሕይወት
መቃብሩ ሞቆን
ኑሮ ብለን ችለን
በሀዘን እሮሮ ሰርገኛን አጅበን

ቀብርን በእልልታ ጧት ማታ አድምቀን
በእንባ ፈገግታና በምጸት ግልፍጫ
ሰቀቅ ደስታን ተክተን
የመቃብር ኑሮን ጸሐይ ዓለም ብለን
የባሰን አታምጣ ከምላስ ለጥፈን
በኮሽታ ባነን
ለኩታራ ሰግደን
ስንቆረጥ ስቀን
ሲጭኑንም ችለን
በለሆሳስ ብቻ እየተነጋገርን
ራስ ቀናን ትተን
ሁሌም ራስ ደፍተን
መቃወምን ትተን
ተቃውሞን ተቃውመን
እምቢኝን ረስተን
ለእምቢኝ እምቢ ብለን
ሁሌም አጨብጭበን
ይሁን እሺ ብለን
ጎሽ እሰየው ብለን
በውስጥ አረን በግነን
ለከሀዲ መንጋ ሀገር አስረክበን
የማይቻለውን በዝምታ ችለን
ፍጹም ትዕግስተኛ ኢዮብን አስንቀን
በቁማችን ሞተን
የባሰን አታምጣ ከምላስ ለጥፈን
ይህም ጥፋት ሆኖ
መዓት ጨመረብን አምላክ ተቆጥቶ
ስለፈጠረንም በሀፍረት ተውጦ::





## <u>ፍርሐት</u>

የጎረቤቴ ቤት በሩ ሲሰበር
ተኩሱ ሲያደነቁር
ኡኡታ በርክቶ
ምድር ቀውጢ ስትሆን
አልሰማሁም ብዬ
አልታየሁም ብዬ
አላየሁም ከቶ
የለሁምም ብዬ
እንስ እንስ ብዬ
ድምጼንም አጥፍቼ
እንቅልፍ አልባ ተኛሁ
የጎረቤቴን ሞት ልሞት ስለፈራሁ
በራሴው ራሴን በፍርሀቴ ሰዋሁ::

## <u>ያኔ</u>

የክራር ጅማት ሲገተር
ቃና ፍለጋ ሲሽከረከር
ንብ አበባን ልትስም
የሚጥማትን ነቅታ ልትቀስም
ጸሐይ ለመውጣት ጉዞ ስትጀምር
ጨለማ ጠፍቶ ብርሀን ሲፎክር
የኮከብ ድምቀት ለሰብዓሰገል ሆኖ ምልክት
የሰውሕሊና መደፈን ትቶ መታፈን ቀርቶ
አቅዋም ሲወስን
የልብ ትርታ ከስጋት ሳይሆን
ለደስታ ብዛት ፍቅርን ሲተምን
ሕዝብ የፈለገው ለዘመናትም የተጠበቀው
ሲከሰት ዛሬ እውነታ ሆኖ

ሲከስት ዛሬ እውነታ ሆኖ
ሳቅም ከልብ ሲሳቅ ዋይዋይታ ተቀብሮ
ሞት ራሱ ሞቶ
ለሕይወት ጣፋጭነት ክራሩ ሲወጠር
ሲቃኝ ሲነካካ
ጣዕመ ዜማው ቃናው ልብን እያረካ
ሲፈስ የደስታ እንባ
ሀዘን ሞቶ አብቅቶ በሀኬት ሲቀበር
ሞት ራሱ ሞቶ ውርደትም ተዋርዶ
የሰው ሰውነቱ በሕይወት ሲከበር
ደስታ ያኔ ነበር።

## መግጠም ከባድ

ግጥም መገጣጠም
አጣጥሞ መግጠም
ክልብሽ ሊል ከጃዩን
ደግፎ አጠናክሮ
እንደገና መግጠም
ቃልን ከቃል ገጥሞ
ቅንጅትን ሰጥቶ
ስንኝ መገጣጠም
ለዛ ውበት ሰጥቶ
እንደገና መግጠም
ሁሉን አንድ አድርጎ
ስልት ሰጥቶ ገጥሞ
ቤት መምታት መገንባት
ቀላል መስሎኝ ክርሞ
ወረቀት ጨርሼ
ለፍቼ ደክሜ
ግጠም ብለውማ





ብለው ግጠምልኝ
ቃል ሁሉ በፊናው
እኔ ራሴ ብሎ
መገጣጠም ጠልቶ
መካለልን መርጦ
ብትንትን አለብኝ።

## ጦርነት

ከመንገዱ ዳር ከጥርጊያው
አይፋ መኪና በሚያልፍበት በአቧራው
ህጻኒቷ ቆመች እጆችዋን ዘርግታ
ከደረቁ ራሽን ቢጥሉልኝ ብላ
ሳቁ ተሳለቁ አንዱ አነጣጠረ
ተኩሰህ እንዳትስት አደራ ተባለ
ተኩሶም አልሳተ ልጅቷ ወደቀች
የወቴን ጭብጨባ ሳትሰማው ቀረች
አይፋ ሙሉ ወቴ ገድሎ ጥሎ ሲሄድ
እሷ ብቻ ቀረች።

## አባይ ማሞ ቂሎ

አባይ ማሞ ቂሎ የመጨረሻ ጅል
የራሱን አስርቦ ሌላውን ያጠግባል
የራሱን አድርቆ ሌላውን ያለግል
ራሱን ሰርስሮ ሰርስሮ ሸርሽሮ
ሌላን ይገነባል።
አባይ ማሞ ቂሎ የጅል መጨረሻ
ዓይነታ መለያ የዘንድሮ ሀበሻ።

## ጊዜ (ለቀድሞዎቹ)

የሰኮንድ እመርታ
የደቂቃ ሩጫ
የሰዓትን ግልቢያ
        ዘለው የቀደሙ
        በሩጫ ያሸነፉ
ጊዜን እጅ ከፍንጅ
ይዘው ወዴት ያሉ
ጊዜን የሰሩበት
በጊዜ የኖሩ
ቀን ቆጠራ ትተው
        የቅምጥ ፍልሰፋ
በጊዜ የሰሩ
ጀብድን የፈጸሙ
እያንዳንዱን ሰዓት በዓመት ያስቆጠሩ
የጊዜን ሩጫ ቶሽ ብለው ይዘው
        ጉዞን የቀየሱ
        ብዙ የተጓዙ
በትንሽ ዕድሜያቸው ብዙ ዓመት የኖሩ
ጊዜን የሰሩበት
እንዳይሰራባቸው ጠጣር የሆኑበት
ጌታ የሆኑበት
ዛሬ እነሱ ጠፍተው
ጊዜ ጌታ ሆኖ
ጌታ ሆኖ ፏልሎ
ትላንትን ይደግማል
ዛሬንም ሰርዞ
ነገንም አግዶ
በሰው ይጫወታል
ጊዜ ጌታ ሆኖ።





## ግጥም ምንድነው?

የስኬት አባዜ ቅንጅት ፍለጋ
ውህደት-ህብረት መሻት
ሺ ምላስ አንድ ላንቃ
ሺ ምላስ አንድ ቋንቋ
የይሆናል ተስፋ
ሁሉ ተዋህዶ
ጠላትን ሲያጠቃ ክንዱን አቀናጅቶ
ሀገር ሲገነባ
ቃሎች ተስካክተው
ስንኝን ገንብተው
ቃና ለዛ አግኝተው ስሜትን ሲነኩ
ነፍስን ሲዳስሱ
ለተተኮሱበት ደርሰው ግብ ሲመቱ
ይህ ሁሉ ግጥም ነው
የመግጠም እውነታ
የግጥም ምስጢሩ
መግጠም ነው መች ሌላ።

## የሕሊና ጣጣ

በጸሐይ ጨረር ተጉዤ
በቀስተዳመና ወገብ ተጠመጥሜ
በቅንድብ ጸጉር
        የእንባን ወንዝ ተሻግሬ
የጡት ተራራን ወጥቼ
ከልብ ደረስኩ ከእምብርቱ
ከነፍስ እምባ ከመሃሉ
ድው ድው ሲል ቢሰማኝ
ዳንስ እስክስታ ነሸጠኝ
ቅብጠት ይዞኝ ስቀናጣ
የደም ጎርፍ ድንገት መጣ

ጦርነም አወጣኝ ከመሀሉ
ከሰው እምባ
ሊደባልቀኝ ከአውሬ ጎራ::

## የሳቅ ሞት

ድሮ በዚያን ጊዜ
ድንጋይ ዳቦ ሆኖ ባጠገበን ዘመን
ሰዎች የሚስቁት ከልባቸው ሆኖ
መሳቅ መደሰቻም ነበር ሞልቶ ተርፎ::
ዛሬ ግን ሌላ ነው ዘመን ተለውጦ
ጊዜ ተበላሽቶ
የሰው ጥርስ ይገጣል
በሳቅ ይሳለቃል
ሁሉም ከአንገት በላይ
ልብም ጥቁር ዋሻ
ዓይን ሁሉ ጥቀርሻ
ዛሬ ዘመን አልፏል
ከልብ የሚስቅ ሰው
ከጠፋ ቆይቷል
ሳቅ ራሱ ሞቷል::

## ቢሆንልኝማ

ቢሆንልኝማ እንደወፍ በበረርኩ
አለምንም ድካም ከሰማይ በደረስኩ
ቢሆንልኝማ ሳልሰራ ባመረትኩ
እዚህ እየሆንኩኝ ያን እዚያ በዳሰስኩ
ቢሆንልኝማ የፈለግኩት ቢሆን
ምኞቴ ቢሟላ ባይጫነኝ ሀዘን
ባይወቅጠኝ መከራ
ቢሆንልኝማ





መሆን የሌለበት ከመሆን ርቆ
ሀዘን ደስታ ሳይሆን ሕይወት የሞት ትርጉም
ጦርነቱ ሰላም ሰቆቃም እፎይታ
ሁሉም ቦታ ይዞ መልኩ ሳይሸፈን
የሚሆነው ሆኖ
መሆን የሌለበት ከመሆን ርቆ
ቢሆንልኝማ የልቤ ተሟልቶ
መሆን የሚገባው ቢገኝ ሆንኩኝ ብሎ
ቢሆንልኝማ ማለት ሁሉ ቀርቶ::

## ከራስ ጋር ጨዋታ

መሬቱ በዓይናችን እየተበሳሳ
ቀና ማለት ፈርተን ለሕይወት ስንሳሳ
ንብረት-መሬት ጭምር ከመብትም ባሻገር
በገሀድ ተነጥቆ ሰብዕናችን ሳይቀር
ጠመንጃ ደግነው ሳይቆርጡ ሰልበውን
ሲቀጥፉ አብረን ዋሽተን
ሀቅን መግደል ለምደን
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን ሞተን
አለና በማለት ሳንኖር እነሆ አለን::

()

ባለታሪክ ሆነን ከጥንት የሰለጠን
ባለአኩሪ ነጻነት ጀግና ሕዝብም ሳለን
ቱርክና ጣሊያኑን ወራሪ አሳፍረን
ለአሜሪካ መስኮብ አልበገር ብለን
ለጥቁሮች አርአያ ማርከሻ ነጭ ሆነን
በጽናት ባንድነት በአንድ ሀገር ቆይተን
ዛሬ በማለቂያው በሽታ ተጠናውቶን
ለፈረንጅ ለጣያት መስገዱ ጀምሮን

ከተቀበረበት እትብታችን ወጥቶ
ሎንዶን ዋሺንግተን ባዕድ ሀገር ገብቶ
ሥሩ የደረቀ ያበቃ ዛፍ ሆነን
ፈረንጅ ሲያሾፍብን ሲረግጠንም ችለን
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን ሞተን
አለና በማለት ስንዋሽ ጊዜ አለፈን፡፡

()

ሕይወቴ ላገሬ ማለት የጅል ሆኖ
የሀገር ቋንቋ ሳይሆን የባዕድ ተወዶ
አንድነቱ ሳይሆን ልዩነቱ ገኖ
ጀግና ለመቃብር ክህደት ለዘውድ ሆኖ
ራስ ቀና ቀርቶ አንገት ደፋ ደርቶ
የወገን ሬሳን ጠቅጥቆ መረመድ
ከእውቀት ተፈርጆ
መጠቆም ማጋለጥ አንጉል አባዜ
በራስ ሳይቀር መጥቶ
ሀገር እሬ ስትል ጆሮን የደፈነ
ብልህ ሰው ተብሎ
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን አልቀን
አለና እያልን በመኖር ላይ ቀለድን፡፡

()

የታሪክ ትዝታ የቀላ ሽብር ቅርስ
የጀግና ምሳሌ የፈሪ ልፍስፍስ
በውርደት መበርከት የሕላዌ ገላጭ
ተጎንብሶ ደንፊ በእውር ዓይኑ አፍጣጭ
ዘመኑ ግርምቢጥ አንድነት-ግንጠላ
በሬሳ ላይ ዘፈን የገዳይ ቅስና
ስንት ደም ፈሰሰ ስንት ሰው አለቀ
ቆሞ መሄድ ቀርቶ ስንቱ ተንፏቀቀ
እንዳይሞት ተዋርዶ በውርደት ግን ሞቶ
አለና ይለናል መኖር ራሱ ጠፍቶ፡፡





()

ሰው መሆን ሰልችቶኝ ሕይወቴንም መኖር
ራሴን ጠልቼው ልሰቅለው ከጅሎኝ
ጥፍሬን ብቻ ሳይሆን ሁሉን ልቆርጥ አምሮኝ
ሰው መሆን ጠልቼ በጨለማ ጉዞ
በሬሳ ዋሻ ውስጥ ሞቀኝ ብሎ ኑሮ
መሮኝ ማጨብጨቡ ለገዳይ መዝፈኑ
ባርነትን ጸጋ ብሎ መቀበሉ
ሰው መሆን ሰልችቶኝ ሰውነትን መካድ
ለአውሬ መገዛቱ ጠዋት ማታ መራድ
እዳልሞት ተዋረድኩ ስዋረድም ሞትኩኝ
መሞቴን ደብቄ አለና እያልኩኝ፡፡

()

ባሕሩም ጠገበ ቀለሙን ቀየረ
ቀይ ነኝ አለና ከጥቁሩ ተለየ
ወፊቷም ጠገበች ዘፈኗን አቆመች
ጸጥታ ዝምታን አድምጡ እያለች
ዓሳም ጠገበና ከተራራ ወጣ
አልገባኝም አለ የመተንፈስ ጣጣ
ግመልም በፈንታው ወጣ ወደደጋ
ለእግሩ ባያመችም አደጋ ፍለጋ
ሰማይ መሬት ሆነ መሬትም ወደላይ
ጉደኳድ ላልሞተ ሰው ሟቹ በአደባባይ
የሕይወት ማር ጣዕም ሬትን አስንቆ
እንዳይሞት ለውርደት ጭራሽ እጁን ሰጥቶ
አለና ይለናል ዝምታን ድምጽ አርጎ፡፡

()

የስማዕት ታሪክ በደም የተጻፈው
ጠመንጃውን ይዞ ሚጠብቅ ከሌለው
ብዕሩን አሹሎ ካጣ ሚጠብቀው
በኢምንቶች ብረዛ ዳግም ይከለሳል
የሰው ልጅ ክቡር ደም ቀይ ቀለም ይባላል
የስማዕት ታሪክ በደም የተጻፈው
ጧፍ ሆኖ ሲያበራ ተኪ ካልጠበቀው
በነፋስ ይጠፋል ሳይለኮስ ከቶ
እንዳይሞት ተዋርዶ በውርደት ግን ሞቶ
አለና ይለናል ነፍሱን ተለይቶ::

()

አባይ ማሞ ቂሎ ለምንጩ ያልጠቀመ
ሃበሻም ጅላጅል ራሱን ቆረጠ
መተማ መቅደላ አድዋም ተረሳ
በይፋ ተሰጥቶ ዙፋኑ ለባንዳ
ታሪኩን የረሳ ሥቃዩን ደጋሚ
አሶሳ በደኖን አረባጉጉን ሰሪ
ሆነና እርምጃ የጓልዮሽ ጉዞ
ወንጀል መደጋገም ሕሊናን ሰርዞ
ጎህን ስንጠብቅ ጸሐይዋ ሸሸችን
የሞቀ መቃብር ጨለማ ዕድላችን
እንዳንሞት ተዋርደን ውርደቱ ገደለን
ቀባሪ ስላጣን አለና እንባለን::

()

ትውልድ ስላለቀ ድልድዩም ተሰብሮ
ሀገር-ባህል ታሪክ ወኔም በዚያው ቀርቶ
አንድ ዓይና የእውር ንጉስ በየፊናው ፈልቶ
የሕዝብ የክት ልብስ የፈረንጅ ድሪቶ
የአድዋ ድል ፍሬ አድሮ ለሶላቶ
የአባይ ልጅ ፖቶማክ ግም ውሃ ጠጥቶ





ሀገር ወዳድነት ስደት ሀገር ጥሎ
ስፒኖዛ ነግሶ ዘረያዕቆብ ቀርቶ
አፈወርቅ ሳይገባን ቫንጎግ ተወድሶ
ፈረንጁ ሲነበብ የሀገር ተረስቶ
ንብ ከተወው ቀፎ እሬቱ ተቀጥፎ
ሕዝብ የተባለውም ሁሌ ጠሙን አድሮ
ዝምቡ ትላትሉ ተምቹ በሀገር ሞልቶ
እንዳይሞት ተዋርዶ በውርደት ተገድሎ
አለና ይባላል ሀቅ አውሪ ሰው ጠፍቶ::

()

በጀርባ ላይ ያለው የጅራፍ ጠባሳ
መብቴ ላለ ሁሉ ዱላ ቁርሱ ምሳ
አንጀት በጣሽ ቁስል ጊዜ የማይሽረው
ታሪክ ቀትር ሆኖበት ጥላ የማይጥለው
የሰው ሰውነቱ ትልቅነት በራስ
አጥንት ሳይቆጠር ሳይወለድ ከራስ
እይታችን መጥቆ ሰማየ ሰማያት
አዙሪቱ ቀርቶ ምድርን ብርሀን ሞልቷት
ይሁን የተባለው ገና ሲሆን ስናይ
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደትም ሥቃይ
አለና እንባለን ሆነን የእንባ ሲሳይ::

()

የታሪከ ቅርሳችን ተረት ነው  ተብሎ
እነአብዲሳ ባልቻን አሕዴድ አስንቆ
አሉላ አባነጋ ሀውልቱ ሁሉ ፈርሶ
የአቡነ  ጴጥሮስም በታጋዩ ጳጳስ ዛሬ ተሰርዞ
በጎጥ መካለሉ አዲስ ፈሊጥ ሆኖ
ጽጌረዳ ጠፍቶ እሾህ ብቻ አብቦ
ለሙ መሬት ሲደርቅ በረሐው ለምልሞ
ሕልማችንም ተኖ ቅዠታችን ደርሶ
ቀንተቀን ቆጠራው መኖርን ተክቶ

እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን ተነን
አለናችን ቀጣይ ከጉድጓዱ ገብተን::

()

ፍቅር ድንገት ነፍሶ ዓይኔን ነካካና
ሳቅ ብጤ አስከጅሎኝ ቶሎም አለፈና
ከልቤ ላይ ደርሶ ነፍሴን ቢፈልጋት
ወግድልኝ አለች ጥላቻ ወሽሟት
ፍቅር ቅንጦት ስሜት የጤዛ መንቲያ
ጸሐይ መጣሁ ስትል ጠፋ ከኢትዮጵያ
ጥላቻ አባደፋር ሁሉን ነፍስ ወሽሞ
እንዳይሞት ተዋርዶ በውርደትም ሞቶ
አለና እንዴት ይላል ከፍቅር ተጣልቶ?

()

ጠባቂ ያጣ ድሀ አራጅ ያዘዘበት
በሽብር በ“ታጋይ“ ደሙ የፈሰሰበት
ተቆርጦ ተጠብሶ ከጉደጓድ የገባ
ቢጮህ ቢማጠንም የሚረዳው ያጣ
በግፍ መሞት ተራ ገዳይ ተሸላሚ
ኢትዮጵያ ጉድ ሀገር ሁሌም አስደናቂ
እንዳትሞት ተዋርዳ በውርደት ግን ሞታ
አለና ትላለች በደም ጎርፍ ተውጣ::

()

አምራቹ አርሶአደር ሚሊሺያ ሆኖ
ገበሬ የሚሆነው ታጋይ ሁን ተብሎ
ሠርቶአደር ጃልሚዳ ለልመና ኑሮ
የለውጥ አጉል ተስፋ ዳንቴሉ ተሰርቶ
እንባላብደም መፍሰስ አላቋርጥ ብሎ
የሀገር ህልውና ገበጣ ጨዋታ





ጠጠሩ የሰው ነፍስ ሲጣል ሚፈነዳ
እንዳንሞት ተዋርደን ስንዋረድ ሞተን
አለና እንላለን ሀገር-አልባ ሆነን::

()

እናቴ ኦሮሞ አባቴ አማራ
አኅቴ ጉራጌ አያቴ ከአድዋ
የልጄ ባል ጉምዝ የእሱም አባት አገው
አገዉም ድብልቅ ከዚህም ከዚያም ያለው
ደማችን ሲጣራ ኢትዮጵያዊ ሆኖ
ለእነመለስ-ሌንጮ ለጠራ ፈላጊ
የማያጠግብ ከቶ

ዜግነት ተነፍገን ጊዜ ተለውጦ
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደትም ሞተን
አለና እንላለን በክልል ተቆርጠን::

()

የታሪክ መጽሐፍ ይዘቱ ቢቃና
ልዑል ራስ ሳይሆን ተራው የሚነሳ
ምን ድንጋይ ጠረበ ንጉሥ ሳሊበሳ
ገባሩ እንጂ ነው ፍዳውን የበላ
ምኒሊክ በአድዋስ ብቻውን ተዋጋ?
ዮሐንስ ብቻ ነው የሞተ መተማ?
የታሪክ መጽሐፍ ይዘቱ ቢቃና
ታሪክ ሰሪ ዋና ያ ተብየው ተራ
የተራው ሰው ታሪክ ያጣው ጸሐፊ ነው
ለመሰራቱማ ታሪክ እኮ እሱ ነው
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን ሞተን
አለና እንላለን ታሪክ ተቀምተን::

()

የሊባ ዓይነደረቅ ስርቆ ሰው ይከሳል
ጅራፍ ገርፎ ገርፎ እሱ ራሱ ይጮሀል
ሰው ቀርቶ ዝንብ አይገል
መንግሥቱ ኃይለማርያም
ቀይ ሽብር ሲካሄድ ገብቶ ነበር ገዳም
ወያኔም ነው አሉ አንድነት ፈላጊ
ዘረኛ አትበሉኝ ባይ ገንጥሎ ገጣሚ
የሆነውን ሆኖ አልሆንኩም ባይ በዝቶ
ገድሎ እየጣለ የሟች አልቃሽ ሞልቶ
የቃልኪዳን ክብሩ ዋጋውም ረክሶ
በአምባገነን ዘመን ውሸት ብቻ ነግሶ
እንዳንሞት ተዋርደን ውርድቱ ጨርሶን
ገለውን ሲያለቅሱ አለና እንባለን::

()

ስፍኖ ነግሶ ሳለ አጼ ምን አጠፉ
በፊውዳል ጨለማ ክብሪቷን የጫሩ
የምርጦቹ ስርዓት ይጥፉ ይውደም ያሉ
ላገር-ለሕዝብ ብለው መስዋዕት የሆኑ
ጉባዔ አዲስአባ ቻርተር ፊርማ ሲባል
ያሉ ውርደት ወግድ ገንጣይ ይጥፉ ይጣል
በጎጥ መደራጀት ፈሊጥ ሆኖ ሲቀርብ
ያሉ ጥበት ይጥፉ ኢትዮጵያችን ትቅደም
ዛሬም እንደትላንት ሲመተሩ ስናይ
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደትም ሥቃይ
አለና እንባለን ከሀፍረት ሳንለያይ::

()

ጉጠት ሳይበጭቀን እኮርማጅ ሳይገርፈን
ወፌ ኢላላ ሳንቀምስ እሳቱ ሳይጠብሰን
በቶርች-ስዮል ዓለም ሳናልፍ ሳንሰቃይ
በአረመኔዎች እጅ ልካችን ሳይታይ





እንዴት እንፈርዳለን በተገኘ ደከሞ
በቃኝ ቢል ቢወድቅ ቢጎዳም ጠቁሞ?
በውሀ ያለ ዓሳ መች ይፈራል እሳት
ሲጠመድ ሲያዝ ግን የሚመጣ መዓት
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደት ግን ሞተን
አለና እንባለን በድን ሆነን አልቀን::

()

ሳይጠይቅ ተወልዶ ለሥቃይ ተዳርጎ
ሀጻን ልጅ ዋይ ይላል ድንገት ነቢይ ሆኖ
ኢትዮጵያዬ ባዩም በትምክህት ተከሶ
ለሞት ይዳረጋል መልሶ ቀልሶ
ፍቅር ይስፈን ባሉ ለሰላም በቆሙ
ጦረኛ ተብለው በጦሩ ተወጉ
የደስታም ህልማችን መከራን ቀፍቅፎ
ዝምታ ጫጫታ ሀዘን ደስታ ሆኖ
ጸሐይ መሬት ወርዳ ብርሀን ፍለጋ
ተኩላ ቤተመንግሥት በግ ወደበረሀ
እንዳንሞት ተዋርደን በውርደትም ሞተን
ቅጥ አምባሩ ጠፍቶን አለና እንባለን::
ሚሊዮን ህልሞችን በቅዠት አፍነን
ማለም ደፋሪውን በሳንጃ ዘልዝለን
እንባ ማንቢያ ዓይኖች ከፋብሪካ አምርተን
የተሰፋን ጧፍ ለኳሽ እጆች ቆርጠን ጥለን
ከእያንዳንዲቷ ልብ ፍቅርን በጥል ገድለን
የቂም በቀል በሬን ጠዋት ማታ ጠምደን
መቃብር ቆፍረን ዘረኝነት ዘርተን
ክፍፍል ጦርነት ሬሳን አምርተን
የማይካደውን ታሪክ ፍቀን ክደን
ለምን እንዴት ባዩን ከአርዮስ ደምረን

ማንም ሳይሮጥ ሸባ ሁሌም ተጠላልፈን
ወደፊትን ትተን ወደኋላ ወድቀን
ከራስ ጋር ማውጋቱን ዝምታንም ፈርተን
አለና እንላለን በቁማችን ሞተን፡፡
እንዳንሞት ተዋርድን በውርደቱ ሞተን፡፡

000

## ደስታ

የምድረበዳ ገነት
የጨረቃ ፏፏቴ
የበረሀ ጽጌረዳ
የቀብር ለት ዳንኪራ
ሳም አለኝ በሰማይ
የረሀብ ሟች ሲሳይ
ማቅ ለብሶ ፍስሐ
ማጥ ገብቶ ጽዳት
የነገ ኮከብ የቀጠሮ
የእንባ ማስታገሻ የእሮሮ
የተስፋ ዓለም የአዕምሮ፡፡





## ጽጌረዳ

(በበረሀ ለተሰዉ ወጣት ፋኖ ሴቶች)

እሾሀ አሜኬላ
ጨንጊት ቁልቋሉ
ምድርን አስጨንቆ
ሞልቶ ተርፎ ሞልቶ
ጽጌረዳይቱ በበረሀ አብባ
በዚያው ትረግፋለች
ማንም ሳያሸታት
በዚያው ትሞታለች
በለጋ ሕይወቷ ታሪክ ትጽፋለች፡፡

## ሰውነት ሲያበቃ

አባብ መርዙን ሲረጭ
አዞ ጥርሱን ሲያገጥ
ነብር ለግድያ ተደብቆ ሲያደፍጥ
ወቴ ታጥቆ በዝቶ አለሁ ብሎ ሲሮጥ
ሁሉንም አይቼ
ሕይወት ይኼ ብዬ
የተደሰትኩ ለታ
ሰውነቴ አብቅቶ
በደስታዬ ጠፍቶ
አውሬነቴ መጣ
አቸንፎኝ ፈካ፡፡

## ስንቱ

ስንቱ ገረጀፈ
ስንቱ ዛፍ ወደቀ
ስንቱ የክት ልብስ ተቀዶ ተጣለ
ስንቱ ጀግና ሞተ
ቡከን ፈረጠጠ
ስንቱ ይሁዳ ፈላ

## ከሀዲ ነገስ

ስንት ሕዝብ አለቀሰ
ሀገርም ፈረሰ
ስንቱ ጽጌረዳ ጠውልጎ ረገፈ
በጉድጓድ እስር ቤት
ስንቱ ንጹሕ ዜጋ ስቃይ ተቀበለ
ስንቱ ከርስ አምላኩ
ሀገር ወገን ሸጦ ለጠላት ሰገደ
ስንቱ ካህን ሞቶ
ቦዘኔ ጠምጣሚው ጳጳስ ነው ተባለ
ስንቱ አፍ ተዘጋ ምላስ ተቆረጠ
ለድፍን አንጎሎች ነጻነት ተሰጥታ
ስንቱ ወንድ አገባ ስንቱ ሴት ተዳረ
የራሳውን ክምር እንዳላየ ሆኖ እየተሻገረ
ስንቱስ አለቀሰ
ስንቱስ ፈነጠዘ
ስንቱ ለጋ አበባ ጠውልጎ ረገፈ
ስንቱስ ለሀገር ሲል ሞትን ተቀበለ
ስንቱ የአፍ አርበኛ ሀገር ጥሎ ሄደ
ስንቱ ሆድ አምላኩ ተጎንብሶ ቀረ
የስንቱ ማንነት ስንቴ ተጋለጠ ?

## መቼ?

የእንባ ጠብታ ጉዞ
የሚፈጀው ሲንከባለል
በመን ይለካል
በሰዓት ነው በቀናት
በወራት ነው በዓመታት?
ለዘመናት ታምቆ ብሶት ሲፈነዳ
መች ጀመረ መች አበቃ
ፍንዳታው ነው መለያው
መጀመሪያው





ወይስ እሜጋው የሰቆቃው?
የልጅ ዕድሜስ መጀመሪያው
ሲረገዝ ነው ሲወለድ
ወይስ የታሰበ ለታ
በሆነበት ታስቦ የሚመጣ?
የሕዝብ እንባ መታበሻው መች ነው
በቃኝ ሲል ሕዝብ
ወይስ እግዜር ሲምር
ትዝ ሲለው በደላችን
ጆሮ ሲሰጥ ለእሮሮአችን?
የሕይወት ሂደት መጨረሻ
መቼ ነው
ሞቶ ሲቀበር ነው
ወይስ በቁም ሲሞት
ህሊና አልባ ሲንጠራወዝ?
የመቼ መቼነት ትርጓሜስ
ምን ላይ ነው ማስፈለጉ
ምኑ ላይ ነው መፈየዱ
መቼ እንዴት ያሉ ደፍረው የጠየቁ
በገፍ ከታረዱ?

## ሰው በበረሀ

በግጨው በረሀ  በወዲምቢው ሀገር
በአላጢስ በረሀ በዝሆኖቹ ምድር
አገኘሁ ባሕታዊ የታጠቀ
ለስደት ለመከራ የተዳረገ
ሰው ክቡር ነው ባለ፡፡
ምነዋ ብቻህን ገባህ ከበረሀ
ብረቱስ ለምን ነው ብየ ብጠይቀው
በረሀስ ከተማህ ብሎ መለሰልኝ
ብረቴም ለአውሬ ነው
ሰው ለሚባል አውሬ ሲልም ገለጠልኝ፡፡

ስው ነኝ ባይነቴ ባዶ ጉራ ውሸት
መሆኑን ተቸልኝ::
በረሀ የስው ልጅ
አውሬ በአደባባይ
ከዚያም በዙፋን ላይ
ሁሉም ነገር ዛሬ ተገልብጦ የሚታይ
ብሎ ሲነግረኝም
ያለው ቢገባኝም
እንደእሱ ለመሆን ቅንጣት አልቃጣኝም::
ቁርጠኝነት ድፍረት የታደሉ ለታ
ከምላስ ባሻገር ለእኔ አልደረሰኝም::

## ሱሰኛ

በእንባ ጠብታ ፍሳሽ
በትንሲቷ
የማን ጥም ሊረካ?
በሰው ደም ፍሳሽ
ከስን ባዘለው
ማንስ ሊደሰት
ብየ ብጠይቅ
አለ አሉኝ የሚጠቀም
በወገን እንባ በንጹሐን ደም
አለ አሉ ባለዛር ባለአጋንንት
የፍጹም ሥልጣን ባለሳምንት
አለ አሉ የደም ሱሰኛ
የሕዝብ ሁሉ መብት መጋኛ
የፍጹም ሥልጣን ሱሰኛ::





## ለእኔ የከበደኝ

ሞትማ ይሞታል አይቀሬ መሰለኝ
የሕይወት ሸክም ነው ለእኔ የከበደኝ
ለእኔ የጨነቀኝ ሰው ነኝ ማለት መሆን
ከአውሬው ተለይቶ ቀና ብሎ መቆም
መሳቅ መቻ አቃተኝ ብዙሀኑ ሲስቅ
የጠላውን አጥቶ
የልቡን አግኝቶ
ፍቅሩን ስሞ አቅፎ
ደስታን ተደስቶ
ለእኔስ የከበደኝ ሀገር ወገን ሲያለቅስ
ሀልው ነኝ የምትል ደስታን ማየቱ::
ለእኔስ የከበደኝ ክህደት ብልጠት ሆኖ
መጎንበስም ድፍረት
መልከስከስም ንቃት
ክብር ሆኖ ውርደት
አለሁ በሚልበት
ቀናቀና ማለት
ማመጽ እምቢኝ ማለት
ከከርሳሙ መንጋ ጭራሹን መለየት::
ሞትማ ይመጣል ተፈራ ተጠራ
መምጣቱ አይቀሬ ነው ለሁሉም በተራ
ለእኔስ የከበደኝ በቁም መሞቱ ነው
ሀገር ወገን ክዶ ሰው አለመሆን ነው::

## መለያው

የሀዘን ማብቂያው መስመሩ
ከልብ አልፎ ልኩ

በአዙሪት ምሬት ናላ ዞሮ
መከራ ራሱ ተጠናክሮ
የማቱሳላን ዕድሜ ተላብሶ
ክረምት በበጋ ላይተካ ምሎ
ባንዳ በአርበኛ ሁሌም ተሳልቆ
ቡከን ተብየም በጀግና አሹፎ
የሰማዕት አጽም ወጥቶ ተሰጥቶ
የሀዘን ማብቂያው ማጠፊያው ጠፍቶ
ሌላ ዙር ፍልሚያ ግድ ነኝ ብሎ
ፋኖው ከአስመሳይ ዛሬ ተለየ
ፈሪን ከጎበዝ ማን አበራየ
የሀዘን ማብቂያው መስመሩ ታየ
የአዲስ ቀን ፋና በትግል ተገኘ ::

## ለደንባራው በሬ

ሽክላ ስኒ ድስቱ
እንስራው ጠርሙሱ
መለኪያው ብርጭቆው
ሁሉም ተደርድሮ
ቦታ ቦታ ይዞ
ተቀናጅቶ አምሮ
ሱቁ በጣም ደምቆ
አይተን ሳንጠግበው
ጠግበንም ሳናየው
ከቤታችን ገብቶም ግልጋሎት ሊሰጠን
ከቶም ሳያደርሰው
የደነበረ አውሬ እብሪት የወጠረው
አናፍቶ ደቅድቆ ከአፈር ደባለቀው::





## ይቅርብኝ መማሩ

መማር ከሆነማ እንጎል ደፍኖ መኖር
ማወቅ ከሆነማ ህሊና ቢስ መሆን
መንቃት ከሆነማ ዓይን ገልጦ መኝታ
መብሰል ከሆነማ የደደቦች ታርጋ
መማር ከሆነማ ሀገር ወገን ሸጦ
ስብዕናን መቅሰፍ ማንነትን ክዶ
ማወቅ ከሆነማ እንእንቶኔን መሆን
ለጠባቦች መንጋ በሎሌነት አድሮ
በወገን መጨከን
በሀገር መጨከን
ይቅርብኝ ልደንቁር ይቅር ባልማረው
ተማረ የተባለው ሰው መሆን ካቃተው::

## መቸ አለትግል

የጎህ ብርሀኑ ጣዕመዜማ
ከምድረበዳ ሲሰማ
የቅርቅሬም ዋይዋይታ የወፍ ቃና
ዘንዶውን ትቶ መሩን ሲያስበላ
አህያ በግራ አናፍቶ ቀኑ ሲሆን ሸጋ
ሞራው ተገልጦ ሲነበብ
የቡና ስኒ አተላ ሲጠና
መልዕክቱ ሆኖ ቀና
መሬት በመድፍ ታርሳ ሬሳ ሲጠፋ
ምለላ ታሪክ ሆኖ
ጥቁር ለባሽ ጠፍቶ
ሀዘን ለቅሶ ተረስቶ
አድነነ ማለቱ ቀርቶ
እንባም የደስታ ፍሬ
ተቃዋሚ ተሸልሞ
ግፍን መኖር ስደት ጠፍቶ

ሲቃይ ሰቆቃ ተወግዶ
ሕዝብም በደስታ ተንፍሶ
ሕይወትም ጣፍጣ ስትበዛ እያጠረች
ማየት አምሮኝ ብነሳሳ
ሞት ጥርሱን አግጦ መንገዱን ዘጋብኝ
ህልምህን አታገኝ እኔን ሳትገለኝ
በቁም ሞቱን ትተህ ና ታገለኝ አለኝ፡፡
ፍርሀቴን ስኖር ለካስ ሞቼ ኖሯል
ጨለማ ሳይጠፋ መች ጸሐይ ይበራል
ታግለን ሞት ካልሞተ መች ሕይወት ይኖራል

## ምን ያስገርማል?

ምን ያስገርማል ግጥሜ ቢጨልም
ዘፈኔም ለቅሶን ሀዘኔን ቢያጅብ
ምን ያስገርማል ፊቴ ቢከፋ
መሳቅ ተስኖኝ እንባን ብቀዳ?
ምኑ ይገርማል ቀጭን መሆኔ
ፍርሀቴ ተርፎ ቢጠፋ ወኔ?
ምኑ ይደንቃል ስድት ቢያስኘኝ
ባላገር ሆኜ ሀገር የሌለኝ?
ምን ያስገርማል ቢጠፋ አዝመራ
ተምች ባገር ሞልቶ ሲጋም ሲበላ?
መን ያስደንቃል ውሸት ቢበዛ
ስንጥቅ ምላሱ ሀገር ሲሞላ?
ምን ያስገርማል ሀገር ብትጠፋ
ጠባቂ ዜጋ ትንሽ ትልቁ እያንቀላፋ?





## ለቅሶ ብቻ

ዓይኔ በእንባ ደንገዘ
በቅን ተሌት ለቅሶ ፈዘዘዘ
እነባ እረኛ የለ እንዳላመርት
በራሴ ለቅሶ እንዳልመገብ፡፡
ምሬት እንክርዳድ ነው ወይስ ስንዴ
ምጸትስ ጨው ነው ወይ በርበሬ?
የእንባ እርሻ ምርት-አልባ
ጉንጭም ፈርዶበት ያው ምድረበዳ
ታጭዶ ጎተራ አይሞላ
እንባውን ዘርቶ ማነው የበላ?
ዓይኔ በእንባ ፈዘዘ ደበዘዘ
የእንባ ፍሬው መና እየቀረ ፡፡

## ሰው በሌለበት

ኮከብ በሀገር ዘንቦ አርፎ በትከሻ
ሽንጥሮው ለጻድቅ በከተማው ውሻ
ሁሉ ልብ ሲከፈት የሞላው ጥቀርሻ
ኮረኮንቹ ፍቅር የእንክርዳዱ እርሻ
ጸሐይ በጨለማ ጨረቃም በቀትር
ዋልካው ሰዳጅ ሆኖ የሚመች ለእግር
ሕልም አሳዳጅ ትውልድ በገፍ ሲጨፈጨፍ
ወኔተስፋሞራል ተገድሎ ሲነጠፍ
እይታ በአፍንጫ በዙሪያ አጥር ሆኖ
የሸቶው ፋብሪካ ቄራ መሀል ገብቶ

ሊማሊሞ ልቦች ባገር ሁሉ ፈልተው
መሪ ኮከብ ሳይቀር ከሰማይ አውርደው

ከብርሀን ንኪኪ ያለውን አውድመው
ተንፏቆ መንዙ ስለት ሳይሆን ቀርቶ
የመኖር ትርጉሙ ያው መዋረድ ሆኖ
ስቃይ መጨማለቅ መበርከት ተወዶ
ከእንቅልፍ የነቃውም ከተኛውም ብሶ
የትላንት ሬሳ የዛሬውን ጋርዶ
የሸሸት አበጋዝ ለአዝማች ተመልምሎ
እይታ በራሱ ጨልሞና ጠቦ
መናኛው ተወልዶ መናኛው ተወዶ
ብዕር የደም ታሪክ ሌላም አልጽፍ ብሎ

ዛሬን ስንሸኘው ትላንት ነገን ሆኖ
ያበቃለትን ቀን ዳግም እየኖርነው
መከራ ሥቃዩን ዳግም እያቀፍነው
እንባን ለማበሻ ጊዜ ራሱ ጠፍቶ
ሕሊናም ራሱ ከጊዜ ጋር ሞቶ
ንብ የሸሸው ቀፎ ያ የእኛ ሰውነት
ገበና ሸፍኖ አጉል መንጠራወዝ
ከመቃብር ገብቶ አጉል መፈራገጥ
የሰው ነኝ ሸወዳ ሰዎች በሌሉበት።

## መሆን ስንችል

መሆን ስንችል ኮከብ ደማቅ የሚያበራ
ትንታግ መሆን ስንችል እሳት የብርድ ጸር
መሆን ስንችል ሻማ ብርሀን ማለቂያ አልባ
ማፍቀር ስንችለ ከልብ ማፍቀር በነፍሳችን
ስንችል ተባይ ማጥፋት ቂም-ጥላቻን ማምከን
ሀዘን ለቅሶን ጠርጎ ደስታን ባገር ማስፈን
ስንችል ሰው ነን ማለት ከትቢያው መነሳት
እረያም አለመሆን ከእንስሳነት መራቅ
ስንችል ለመሆን ከርስ አምላኩ ጭራቅ
አብሮ መኖር ስንችል በውዴታ አንድነት





መጥበብ መካለልን በህብረት ማስወገድ
ስንችል በራስ መኩራት በአክሱም ላሊበላ
በጎንደር በሐረር በጋሞ ሲዳማ
ስንችል በራስ መኩራት ለነጭ አለመስገድ
ክብርን መከላከል ውርደትን ማስወገድ
ሰው መሆን ስንችል ልቡ ያልከሰለ
ነፍሱ ያልጎበጠ ለነፍጥ ያልሰገደ
ሰው መሆን ስንችል ተባብሮ ተፋቅሮ
በሰው ሰውነትን ከሰው ተደባልቆ
መሆንን ስንችል አለመሆን መርጠን
ሰው መሆን ሲገባን ሰው መሆን አቃተን።

## ፍቀዱልኝና

ፍቀዱልኝና ህልም ልይ ሳልተኛ
አትቆጡኝና ወደሰማይ ልሸና
አትናደዱብኝ በአምላክ ላይ ልቀልድ
ቂም አትያዙብኝ ድህነትን ብወድ
በማይነጥፍ ተስፋ ሀዘንን ባስወግድ
ለቀቅ አርጉኝና ጨረቃን ልዳስስ
ፊታችሁ አይቆጣ ልቤን ባለሰልስ
ፍቀዱልኝና ፍርሀቴን ልግደል
አንገቴን አቅንቼ የልቤን ልናገር
ገዢዎችን ልተች መንግሥትን ልቃወም
አትናደዱብኝ ጉም የያዝኩ ቢመስለኝ
ጭራሽ አትከፉ ቃልኪዳን ቢከብደኝ
ቂም አትያዙብኝ ቂምም ቢዘውረኝ
ተዉ አትታዘቡኝ እልክ ቢሸፍረኝ
ፍቀዱልኝና ህልሜን ልኖር ልመኝ
ቀን ያላለፈለት ሀበሻ እኮ ነኝ።

## ለሰላም

ለገዳይ ጦርነት ልዘፍን መች ፈልጌ
ለባለነፍጥ አውሬ መዝፈን መች ከጅዬ
ሰማይ ቢገለበጥ አልዘፍን ለክላሺኔ።

እንዝፈን ካላችሁ እንዝፈን በጋራ
የጎስቋላው ደሀም ድምጹ ያስተጋባ
እንዘምር ለሰላም እንጩህ በጋራ
የግፍ የእልቂት ዘመን ለሁሌ እንዲያበቃ
እንዝፈን ካላችሁ ለሰላም እንዝፈን
በጋራ ተነስተን በአንድነት ተሳስረን
እንዘምር እንዝፈን ሰላምን እንጥራ
የጦርነት መዓት ከሀገራችን ይጥፋ
ለሰላም ለኢትዮጵያ ተባብረን እንዝፈን
መዝፈን ብቻ ሳይሆን በጋራ እንታገል
አለቆራጥ ትግል ሰላም አይታደል
እንዝፈን ካላችሁ ለሰላም እንዝፈን
የጋራ ዘፈኑን በትግል አጅበን፡፡

## አዲስ ሰዎች

አሉ አዲስ ሰዎች በአዲስ የተሰሩ
እባብን ቢነክሱ መርዘው ሚገድሉ
ደስታን በሀዘን ገንዘው ሚቀብሩ
በህጻናት እንባ ጥምን የሚያረኩ
አሉ አዲስ ሰዎች ገድለው የሚያለቅሱ
ከመከራ እርሻ ሬሳ የሚያመርቱ
አሉ ጭራቅ ሰዎች በአዲስ የተሰሩ
ውድ ሀራቸውን ጭራሹን የካዱ
ለባዕድ ለጠላት መስገድ የመረጡ
አዞ ቢነክሳቸው ጥርሱን የሚሰብሩ
ልበቆርፋዳዎች በረዶ የሚደሙ
ለቅሶ በበዛበት እስክስታ የሚወርዱ
አሉ አዲስ ሰዎች በአዲስ የተሰሩ
በሳቅ በፈገግታ ገድለው የሚቀብሩ
ዘመቻን አውጀው ሽሽት የሚመርጡ
ሰላም ሰፍኗል ብለው ቃታ የሚስቡ





ወገን ሬሳ ላይ ኑሮን ሚገነቡ
ከመቃብር ቦታ ግብር የሚጠሩ
አሉ አዲስ ሰዎች ሞተው የሚኖሩ
እባብን ቢነክሱ መርዘው ሚገድሉ፡፡

## ቁጭት

ብዙ የተማሩ ብዙውን ያጤኑ
ብዙ ያነበቡ ማዳመጥ የሚያውቁ
ምላስን ሸብበው ጆሮን የሚከፍቱ
ከትንሽ ትልቁ ከሁሉ የሚማሩ
ቀና አስተማሪዎች ትህትና የለበሱ
ዛሬ ወዴት ጠፉ መቸ ለት አለቁ
ማንም ሰው ሳያውቀው በቅሎች ተተኩ
አንጎል ባዶ ሆነው ጉራን ባነገቡ
በግልብ ገለባዎች መቸ ለት ተተኩ
እኒያ የሰው ሰዎች መቸ ለት አለቁ?

## የዘንድሮ ደስታ

በቀን ሁለት ጊዜ ብቻ አልቅሼ
በሳልስት አንዴ ተመግቤ
በቀን አንዴ ብቻ ተገርፌ
በወር ሁለቴ ብቻ ታስሬ
በቀን አስር ሰው ብቻ ቀብሬ
በወር አንዴ ቆስዬ
በቀን አንዴ ለግዴታ ሰልፍ ወጥቼ
በአንድ ሌሊት አንዴ ብቻ ቃዥቼ

ሕይወቴ ተርፋ ከሥራዬ ብቻ ተወግጄ
ከሀገር እንዷቷን ክፍል ብቻ አስገንጥዬ
ሌላ ሌላውን በክልል ቀጠሮ አቆይቼ
ሕይወቴ ተርፋ መብቴን አጥቼ
ደስታን ያገኘሁ መሰለኝ
ነገን ፍርሀቱ አስበረገገኝ
ሀቅን ማመኑ ትግል መድፈሩ እያሰጨነቀኝ::

## አንዳፍታ

ኖህማ ሞኝ ነው በዝምታ ገንቢ
ቢሳለቁበትም ሳይሸበር ገፊ
የኢዮብማ ትዕግስት ለሽሙጥ ያመቻ
በመጨረሻ ግን ማነው ያቸነፈ ?
የሀገር ግንባታ የማቅናቱ ሚና
በዘመኑ ርዕዮት በጦርና ጋሻ
በዋይዋይታ አጀብ በግፍም ተራራ
መንደር እየጋየ ሕይወት እየጠፋ
ወራሪ ተጠቂው ውሎ አድሮ ድብልቅ
የሂደቱ ጎማ ሁሉን ሚጨፈልቅ
ከጋመው እሳት ውስጥ ሀገር ቀልታ ፍማ
ተጎትታ ወጥታ በሕዝብ ተቀጥቅጣ
በሐረርጌ ሾላ በኢሉባቦር ጎብጣ
ሲዳሞ ድቡልቡል ሰሜኑ ተራራ
ትስስሩ በደም ሲፈስ በከረመው
ዛሬም በየዜጋው ደም ስር የሚሮጠው
ትስሰሩ ታሪክ ጸጋ መርገም ሁሉ
አኩሪ አሳፋሪ ሀገራዊ ገድሉ
አብሮ የተደማ በጋራ የተሰራ
የጀግንነት ታሪክ ሁሉን የሚያኮራ
አብዲሳ ምኒሊክ ዮሐንስ አሉላ
ጣይቱ አሰገደች አያሌ ሴት ጀግና
ሀብተጊዮርጊስ ጓንጉል ታከለና ባልቻ
እስላም ክርስቲያኑ ዛፍ አምላኩ ሌላ





በአራቱም አቅጣጫ ለሀገር ሟች ዜጋ
ጠላት አሳፋሪ ወራሪ አሳፋሪ
ለጥቁር ሕዝበ ሁሉ ነጻነት አብሳሪ
ነበረን ታሪክ በጣም የሚያኮራ
ዛሬ ዛሬ ሆኖ ተካደ ተረሳ::
ያንን ታሪክ ትተን አኩሪ ታሪከ ጥለን
ቡትቶ መናኛ ድሪቶ እየመረጥን
የእንግሊዝ ሰበካ የአሜሪካን መዘዝ
የጣሊያን የጀርመን የስዊድኑም መርዝ
ታሪክን አስክዶ በእርቃኑ እያስቀረ
የዓይጥ አንባሳነት ዛሬ ተነገረ
ቡከኑ ኢምንቱ ተሰልቦ አስረገዘ
የአንበሳ አንበስነት በስም ብቻ ሆነ ::

ኖህማ ሞኝ ነው አሉላም ወራሪ
ምኒሊክ ጸጋ አጣ አሉላም ተራኪ::
ጽጌረዳ ረግፋ ሾሁ ተስራጨ
ሽቶ እየተደፋ ግም ባገር ተረጨ
ታሪክ ተሰረዘ ሀገረም ተካደ ::

ክህደት እምነት ሆኖ ክታብ ተበጠሰ
በደኖ አርባጉጉ ሬሳ ታረሰ
ጨለንቆ የተባለው ቋራ-አረካ ሆነ
ያለፈ ላይመጣ ወንል በረከተ
ስንቱ ጮሌ ንዑስ በሕዝቡ ነገደ
ካናዳ ተኩሶ ወለጋ ገደለ
ዋሽንግተን ሆኖ ገፈርሳን ወረረ
ለንደን አምስተርዳም ፋኖ በሉኝ አለ::
ስንቱ ምናምንቴ በምላስ ጦርነት
በቅጥፈት በውሸት በሩቅ ሆኖ ጨኸት
ለሀገር ጠላት አድሮ ገንዝብ በማካበት
በጥላቻ ዲስኩር ሕዝብን በማጋጨት
ስንቱ አስመሳይ ታጋይ በሕዝብ ቀለደበት
ያን ምልዐተ ሕዝበ ያን የፈረደበት
ኧረ ስንቱ ጮሌ ስንቴ ጨፈረበት

ስንቱ አጉል ነጻ አውጪ ስንቱ ነገደበት::

ዋህማ ሞኝ ነው በዝምታ ገንቢ
ቢሳለቁበትም ሳይሸበር ገሬ
የኢዮብማ ትዕግስት ለሽሙጥ ያመቹ
በቃል ኪዳን አፍራሽ ሁሌም የተተቸ ::
ማንነት ሳይጠፋ ልፋት ከንቱ ባይ
የዓይጥ አንበሳነት እንዲያው ቅዠት ቀሮ
አጉል ጨዋታ የሚያስቀር ቀስሮ::

0 0 0

## ሰብዕና

ምንኛ መንገዱ ቢሆን ጠመዝማዛ
ክርችም ድርግም ብሎ መግቢያው በር ቢዘጋ
ምንኛ ከማጡ ገብቼ ብቆሸሽ
ወደፊትን ትቼም ወደኋሊት ብሸሽ
ጀግና ሊቆጠር ሲል በቦታው ባልገኝ
እኔ እኔ ማለቱም በፍርሀት ቢያስውጠኝ
ምንኛ ብጠቁር ብሆን ፍጹም ድሀ
የምበላው ያጣሁ የምጠጣው ውሀ
ቡትቶ ድሪቶም መልበሱ እሮብኝ
ሙጃሌም በእግሮቼ ቤቱን ቢሰራብኝ
ምንኛ ጆሮዬ በዲስኩር ቢዘጋ
በዝምታ መቻል ቢባል የእኔም ታርጋ
ከቶ ማንነቴን በልቤ ባቆየው
የራሴ ጌታ ነኝ የሕይወቴ እለታ
ነፍሴን ከቶ የማልሸጥ የመጣ ቢመጣ::





0 0 0

# ክፍል ሁለት

## ዘንድሮ

## በሚገባን ቋንቋ

አማርኛ ብለን
ኦሮሚፋ ብለን
ጉራጊኛ ብለን
ብለን አገውኛ
ከዚያም ሶማሊኛ
ሲዳማ አፋርኛ
ሌላም ሁሉ ቋንቋችን ነው ብለን
ተሞኝተን ከርመን
ንቃት ጎድሎን ባጅተን
ከርመን ተደናግረን
ነጻ አወጪ መጣልን የሚያነጋግረን
የክላሺን ቋንቋ
በልዎ በልዎ
የቦምበኛ ቋንቋ
ጸንቶ የሚያሰተምረን
ገድሎ የሚያናግረን
በሚገባን ቋንቋ የሚያነጋግረን::

## ለእኛ የደነቀን

በረሀብ አድመኞች ምን ያስገርመናል
ሚሊዮን በጠኔ ሲረግፍ አይተናል
ወዲከውሊ ሱዳን ብዙ ሺ ቀብረናል::
አርባ ተገደለ ስድሳ ሰው ታረደ





ጸጋዬ አብርሀም ይስሐቅ ታሰረ
ጋይም ተገደለ እገሌም ታረደ
እልቂት ተፈጸመ ምን ያስገርመናል
በሬሳ ክምር ላይ ተጉዘን መጥተናል
ገድለን የጣልነውን መቁጠር አቅቶናል::
ለእኛስ የገረመን ያስደነቀን ጉዳይ
የወሲብ መጽሔት ሲሸጥ በአደባባይ::
ሀገር ባፈተታት ትስንጠቅ ትለያይ
ሕዝብም ባዘዝንበት ይወገር ይሰቃይ
ይህ ሁሉ መች ሆኖ አስገራሚ ጉዳይ
የወሲብ መጽሔት ሲሸጥ በአደባባይ
ሀገር እንኳን ባይኖር ባህልን ሲያደባይ::
ይህ እንጂ አስገራሚ እኛን የሚያሰቃይ::

## ነጭማ ነጭ ነው

ነጭማ ነጭ ነው
ሁሌም ልንጭህ ይላል
ብርሀን ነኝ ሥልጡን
ገብሩልኝ ይላል::
ነጭማ ነጭ ነው እንግሊዝ አሜሪካ
ባርነትን ሚመኝ ሁሌም ለአፍሪካ::
ነጭማ ነጭ ነው ማንነቱ ይፋ
ቅኝ ገዥ አረመኔ
በዝባዥ አይታክቴ
ጸረ ጥቁር አውሬ::
ነጭማ ነጭ ነው
የምናውቀው ሰይጣን
እኛን የፈጀን ግን ጥቁር የእኛው መሳይ
ራሱን የጣለው
ለፈረንጅ ያደረው
ገንጣዩ ጠባቡ

## ክልል

እኔን አግኝቼ በመስተዋት
ስንጥቅጥቁ በወጣ
ሁለንተናዬ ተገንጥሎ
በየፊናው ኮብልሎ
በክልል ተለያይቶ
ማነን ልለው ቃጥቼ
ቋንቋው ቢጠፋኝ መግባቢያው
ተለየሁተኝ አልቅሼ
ስንጥቅ እኔ
ብሳሽ መሆኔን ተረድቼ::

## መቼ አበቃና?

መቸ አበቃና ታሪኩ
መቼ ተፈጽሞ ገድሉ
መች ተዘጋ ምዕራፉ
ያ ሕዝባዊ ገድሉ?
መቼ አከተመ የደም ግብር
መች አለቀ ሥቃዩ
መቼ ሀገር አለች እረፉ
ለእኔ ስትሉ አትልፉ?
መች ተሰበረ የከርቸሌ በሩ
መች ተዘጋ ጉድጓዱ?
የታለና ወያኔ የተነነው
አረመኔነት ያከተመው?
መች አበቃ ጦርነቱ
የተቃውሞ መጣሳቱ?
የት አየን ግብዞች





ከሥልጣን ሲወርዱ
መቼ ተኩላ ወጣ ከኢዩቤልዩ?
መቼ አበቃና ሁሉ ጉዱ
ሰላም መጣልን ሲሉ ሰበኩ?

## ለእነ ጸጋዬ

ባልሰማ ይሻለኛል ሀቁ
ያ የደረሱበትን
ባላውቅ እመርጣለሁ የእነሱን ሰቆቃ
የአዕምሮ ሥዕሌ ዋጋ እንዳያጣ::
ባልሰማ እመርጣለሁ የሆኑትን
ስፈራ ስቸር ምገምተውን
አልስማ እውነታ ሀቅ ምትሉትን
ተስፋን በደረቅ መሬት ምትገሉብትን::
ይቅርብኝ ለእኔ ግምቴ
ይቅር ከእኔ ጋር ምኞቴ
ሞት ሥቃይን በሳቃቸው ረቱት ማለቴ
የሚውጣቸው ጉድጓድም
ሊቆፈር አይችልም ማለቴ::

## የአብዮት ልጆች

መጣልን ባይ ተጠቃሚዎች
ሚፈነድቁ ጮቤ ረጋጮች
የአብዮት ልጆች ሁሌ ሚጠግቡ
ከሬሳ ክምር ከርስ ሚሞሉ::
መጣልን ባዮች ተጠቃሚዎች
ሀቀኛዎቹ የአብዮት ልጆች
የሀገር ምስጦች::

## ተስፋ አልባ

በተስፋ የሚኖር በምኞት ይሞታል
ሳይተኛ የተኛም ሲነቃ ይወድቃል
በሀሳብ ዘመቻ ጦር የመዘዘውም
የቃላት አዳፍኔ ከአውሬ አያድነውም::
የምላስ ጦረኛ የሶፋ ላይ ፋኖ
ጥይት የጮኸ ለት አይገኝም ከቶ::
ግራ ቀኙን ተቺ ተግባር አልባ ጮሌ
ሲሟሟ ጤዛ ነው እያመች ለወሬ::
ለፈረንጅ ያደረ የአንድነት አርበኛ
የእነአጅሬ ወንድም የክህደት ሱሰኛ
ባንዳነት ባንጎሉ ሲሾር የከረመው
ለአንድነት መጋኛ መሆኑ አይቀሬ ነው::
ዓይኑን ከፍቶ ሚቃዥ ርግማን የሚያልም
ትግል ጠሩ ቢሆን ከቶ አያስገርምም::
በተስፋ የሚኖር በምኞት ይሞታል
አጉል መፋዘዝም ቀንበርን ያጠብቃል::
ይህ ሁሉ ሀቅ ነው ወይስ አጉል ግራ
ምን ይፈይዳል ሰው አለተስፋ ጮራ?
ከጨለማው አልፎ ብርሀን ማይታየው
ሀቅን የተረዳ ዓይኑን የከፈተ

ተስፋ–አልባ በድን በቁሙ ወይስ የሞተ ?





## ክፉ ቀን

ድምጽ ሳይሰማ ተጨናግፎ
ብሶት ሳይሰማ ታፍኖ
ዝምታ ከብዶ ሲንጫጫ
እንባ መፍሰስ ፈርቶ ሲገታ
ምላስ ታጥፎ ባለቤት ሲያንቅ
እግር ጉዞን ፈርቶ ባለበት ሲረግጥ
ልብም ድውድውን ሊደበቅ ሲሻ
አንጀት ዝርግ ሆኖ ቁርጠት ሲያመጣ
ለራስ ክስ መዘዝ ጣትም ሲቀስር
አላይም ብሎ ዓይንም ሲደፈን
አላስብ ብሎ አንጎል ሲደፈን
ጆሮም ላይሰማ በአጥር ሲዘጋ
የሰዎችም ሆድ ረሀብን መርጦ ምግብ ሲጠላ
ሆንኩኝ ያለውም አልሆንን ሆኖ
ሞትም ገች ሲል ሕይወትን ነጥቆ
ጸሐይዋ ወጥታ ብርሀን ሲጠፋ
ከዋክብት ደምቀው ደይኑ ሲስፋፋ
ሕዝብም እያለ ሀገር ስትጠፋ
ገንጣዩም ሲነግስ ጀግና ሳይጠፋ
ሊባል ይገባል ዘመኑ ከፋ
ክፉ ቀን መጣ::

## ያልነበረ ሲገኝ

ከጭቆና ተረፍ መረፍ
በልቶ ፍርፋሪ
ጨቋኝ አረመኔ ሲባል የከረመው

አዲስ ፊት ተሰራለት
ሌላ ስም ተገኘለት
ኖሮ ለካ ተደብቆ
በጭቆና እሱም ሳይቀር ተደቁሶ
በነፍጠኛው ተደቅድቆ።

ደቀስጢፋ መንኩሶ ኖሮ
ባሕርዳር ላይ ድንገት ታየ
ጭቁን አማራ ተገኘ
አማራም በመደብ ተለያየ ።

## ያለፈው ይሻለኛል

ታሪክን እወዳለሁ ያለፈ
ባፈተተኝ ተስታዋሺ
ቢያሻኝ ደግሞ ተከሳሺ
ተረሺ።
የመቶ ዓመት የሶስት ሺ
እንዳሰኘኝ ተቀናሺ
ተለዋጪ።

ታሪክ ይሻለኛል ያለፈ
ጠባቂ-አልባ ተቆርቋሪ
ተጨራማች ተሰባሪ።
ዛሬማ ክይሲ ነው ግትር





አስጨናቂ የነገ አጥር
የነበርንን ነጋሪት ሰባሪ
እየኝ ምላሽ ስጠኝ ባይ ደባሪ
ካልጨበጡት ነገን ሳይቀር ነፋጊ።

## የሶፋ ዘመቻ

ቃላት ጥይት ሆነው
ምላስም ጠመንጃ
ጉድብ ሶፋ ሆኖ
ኮኛኩም የደም ጎርፍ
መለፍለፍ መተቸት ማለምን ተክቶ
ምላሽ ተኩስም ጠፍቶ
መንጣጣት በርክቶ።

ጀግናው በረከተ
ፋኖው ከፋኝ ባዩ
የቁጭ እሰኳድ በዛ
የርቀት አዋጊ
የወሬ አርበኛ
የምላስ ማራኪ።
ጠላት ልቡ ሞላ
ገጠምኩህ የሚለው በሩቅ ስለተኛ።
ከወሬ ባሻገር ከሶፋ ዘመቻ
ትግልን ስለፈራ።
የሚነካው ጠፍቶ
ጠላት ልቡ ሞላ።

## የነገ ቡከን

ዊስኪ ኮኛኩን ጠጣሁ ጨለጥኩት
ብሩንዶ ክትፎ ሁሉን ወጠቅኩት
ሰማይ ከመሬት ተገናኘልኝ
ሁሉም ቀለለ ብናኝ ሆነልኝ::
ጎራው አሰኘኝ በጣሙን ሸለልኩ
ቼ በለውን ሳልታክት ዘፈንኩ::
በስካር ፈረስ ወዲያው መጭ አልኩኝ
ከወትሮው አኔም ጥል ተያያዝኩኝ
በመጠጥ ወኔ ቡከንነቴን እየረሳሁኝ::

## ሰላም

ሰላም ደምቃ ፈክታ
ቤተመንግሥት ገብታ
ከራዲዮም ውጪ
          አልገኝም ብላ
ዱር ገደል ጫካውን ለጦርነት ትታ
መነከሰች አሉ
          ዋልድባ እያለሳት
ቤተመንግሥት ገብታ::

## ብርሀን

የጸሐይ ሆነ የኮረንቲ
ጠፊ ብርሃናቸው ተተኪ
ዘላቂነትን ናፋቂ::
ብርሀንስ የልብ ነው የደመቀ
የህሊና መብራት ያልደከመ ::
የወገኔ ባይ ሀገሬ ባይ ፍንጣቂ





ቦግ ያለና ዘላቂ
የማይጠፋ መንገድ መሪ::

## ሐውልቲቷ

የነጻነት ሐውልት የአሜሪካ
ነጭ ናት አለት ድንጋይ
ልበ-በድን የላት ዓይን::
ለባርያ እንባ አትበገር
ጥቁር ሲፈጅ ማትሸበር
ሐውልት ናት በድን ድንጋይ
ብርሀኗ ለነፍሰገዳይ
እውር ዓለት ምንም ማታይ::

## ነፍጠኛ ላም

ታስራ ተጠፍራ ላሚቷ
በግድ ተጉዛ ትግራይ ገብታ
የክልል ቋንቋ አላቅ ብላ
ባ ብትል በአማርኛ
          ይች ትምክህተኛ
ነፍጠኛ ተብላ ተወገረች
ሳር በሌለበት በረሀ ተሰደደች::
ዘር ቋንቋ ሳያጣሩ የዘረፉ
ሳይቀጡ ያጓጓዙ
ድሀ ላሚቷ ፍዳ አየች
በምታውቀው ባ ባለች::

## አማርኛ

“ድንገቱ“ ደረሰ ማንም “ሚተይበው“
ዛሬ “ቅቡል“ ሆነ
“ግንባር-መስመር“ ሀገር ስልፉን አፈረሰ
“የሚስተገበረው“ እያደናገረ
“ታዳጊ“ ወጣቱ አዳጊነት ትቶ “ሰለባ“ እየሆነ

ከአጸደው ተባሮ “መዋዕለ “ ገብቶ
“ጢያራውም“ በሮ
“ራቢጣው“ ጮኸ
ሲዘገብ “ሲተየብ“
የአማርኛው ትርጉም ሀገር ጥሎ ጠፍቶ።

## እብዱ ማነው?

እብዱ ማነው?
ጨርቁን የጣለ
ናላው የዞረ
ብሎኑ ሳልቶ
ውሉን የሳተ ?

ማነው እብድ የለየለት
ራቁት ሂያጁ
ድሪቶ አሮብን ጥሩ ለባሹ?
ቋንቋኛ አውሪው?
ሱፍ ለባሹ የተሞሸረው
ሀገሩን ካጄ ልቡ የሞተው?
ራቁት መሆን ካሳባደማ





ህጻኑ ሁሉ
ምልዓተ-ሕዝቡ
አማኑኤል ገባ።
ያበደስ በእውነት ውሉን የሳተ
ሀገር ወገኑን ሁሉን የካደ
በንጹሐን ደም እየነገደ
ለአምባገነኖች እየሰገደ
ልብሱን ተላብሶ የተራቆተ ።

## ቅብጠት

ዛፍ በረረ ወፍን ፍለጋ
እምታርፍበት እምትዘፍንለት
ፍየል ነጎደች ነብር እያለች
ፍርሀት ናፍቋት ሞትን ፈለገች።
አህያ አናፋ ጅብ ናልኝ እያለ
በልቶ መተኛት ደበረኝ አለ ።
ሀበሻ አበደ ወያኔን ጠራ
ሀገር ረስቶ ደርግን ቢጠላ
ትሻል እያለ ትብስን አገባ

ውሎ ሳያድርም መቀመቅ ገባ
ውርደት ለበሰ ሀገሩን አጣ።

## ሀበሻ

በበረሀ የሚበርደው
ሞቻ ገብቶ የሚሞቀው
ጠኔ ይዞት የሚጠግበው
ሳይጠጣ ጥሜት-አልባ

ሀዘን ውጦት ሳቂታ
ተቀምጦ ብቅል አውራጅ
ሲንጠራራ ተጎንባሽ
ትላንት ሞቶ የዛሬ ሰው
በነገ ላይ የሚያሾፈው
ብልህ መሳይ ተላላ
ሞኝ መሳይ አራዳ
ሀበሻ ነው ሀበሻ ነው
ትላንት ሞቶ የዛሬ ሰው
በነገ ላይ እያሾፈ
በራሱ ላይ ሚቀልደው።

## ታሪክም ይረሳል

የታሪክ ጎማ ባለፈበት
መሬት በእንባ-ደም ከራሰ
ታሪክ ተጽፎ ባለፈበት
ብራና ወረቀቱ በበደል ከተጨራመተ
ጥላቻና ግጭት
ትንቅንቅ ጦርነት
የተውሶ ጥይት
መንደሮች መጋየት
ሥቃይ-ውርደት ስደት
የሺዎች መፈጀት
ከሆነ ታሪኩ
የታሪክ ዋና ገጽ በፍቅር ሳይገለጽ
በሰው ደም ከራሰ
በቀል ከታፈሰ
ታሪክ ይዘለላል
ከቶም ባይረሳ ወደጎን ይተዋል
ብዙ ሌሎች ሕዝቦች ይህን ተረድተዋል።
ሀበሻ ግን ሌላ ያልታደለ ሆኖ
ታሪክ አገላብጦ ተረቱን አላምጦ
የጥላቻን ምዕራፍ ይደግማል አክርሮ።





ጊዜ የቀበረውን ቆፍሮ ያወጣና
አሳዛኝ ታሪክን ሊደግም ይባዝናል
ይላል ደፋ ቀና።

## ጉድ በነፍሴ

ነፍሴን ጉድ አገኛት መጸለይን ተውኩኝ
አማኝ መሆኔንም እየጠረጠርኩኝ።
ታጋይ የነጠረ የስላ ዘረኛ
አቡን ጳጳስ ሲሆን
ቁራንም ያልቀራው
በዘር ታርጋ ብቻ
ሙፍቲ ሲባል ሲሾም የሻሪያም ዳኛ
ጉድ ዓይቶ ዓይን ያልኩት
ልቤን አስጨከነ
ጸሎት ከንቱ አሰኘኝ
ነፍሴንም አስረሳኝ
ማመን ምን ሊፈይድ
እያለ አናጋኝ።

## ለሩቅ ሀገር ፋኖ

እዚህ  ናና እስቲ አሳየኝ
ጀግና ሰው ሞልቷል እስቲ አሰኘኝ።
ና ና ተጠጋ እጅህን ዘርጋ
ልዳሰው ልንካው የጥይቱን ብስ
ያንን ጠባሳ።
ና ና አሳየኝ ውጣ ውረዱን
ተጉዘህ አይተህ (ሀቅህ ከሆነ ) የለመድከውን።
ና በለኝ ተዋጋ ጦሩን ሰብቀህ
ና በራስህው እጅ ጠመንጃ ይዘህ።
በራስህው እጅ ጠመንጃ ይዘህ።
ና አስተዋውቀኝ ትግል ከምትለው
የፈራ ልቤን ድፍረት ያድምቀው።

ናማ አሳየኝ ታገል አታግለኝ
እንዲያው በሩቁ ከምታደርቀኝ
በጽሑፍ-በካሴት ከምታቸከኝ
ናና አታግለኝ
ክፉ ደጉንም ና ተካፈለኝ
በሩቅ ርቀት ከምታደርቀኝ።

## እንጳፍ ግጥም

እንጳፍ ግጥም
የእነተስፋዬን ተስፋ ያቀፈ
የአምሀን አምሀ የወረሰ
የጸጋዬን ጸጋ የለበሰ
የእነአበራሽን ብርታት የቀመሰ
የእነጋይምን ትዕግስት የታገሰ
እንጳፍ ግጥም የቀላ
በእነዳዊት ደም በእነአብደላ
እንጳፍ ግጥም የሰላ
የጨቋኝ መንጋን የሚቀላ
የነጻነት ክቡር ዜማ
የመብት የሰብዕና ማወደሻ
እንጳፍ ግጥም መቀስቀሻ
ሰወን ለሰውነት መጋበዣ
የባርነትን እንቅልፍ ማስወገጃ
ቅሌት ውርደትን መሰረዣ
ፍቅር ተስፋን መቀስቀሻ
ክፋት ጥላቻን መጨረሻ።
እንጳፍ ግጥም
የተስፋዬን ተሰፋ
የጸጋዬን ጸጋ
የሰማዕትን ክብር መላበሻ።





## ተዓምረ-ክልል

የክልል ፖለቲካ ትሩፋት
ጸጋው ቤዛው በዝቶ
በትግራይ ክልል አንድ ተትረፍርፎ
ምድረ ሀበሻ ግሩም አለ
ተዓምር እያስተዋለ
የክልል አውሬ ሁሉ ጨምቶ
ጅብ ከክልሉ አህያ ጋር ተፋቅሮ
ነብርም ከክልሉ ፍየል ተጋብቶ
ለክልል ባዳ ብቻ አውሬ ሆኖ
ምድረ ሀበሻ ግሩም አለ
በየክልሉ እያጉተመተመ
የገዢ ሥልጣን ክልሉን
ሚነግረን ጠፋሳ እያለ።።

## አጉል ክስ

በጠራራ ጸሐይ በመንገዱ
ተደብድቤ
ተዘርፌ
ለሆስፒታል ተዳርጌ
ዱላው ነው መስል ያፋዘዘኝ
ያጃጃለኝ
ደብዳቢዬን መክሰስ ያስከጀለኝ
ታጋይ መባሉን ብጻይ ያረሳሳኝ
ለቀጨኔ ፍርድ ቤት የዳረገኝ
በስም ማጥፋትም ያስከሰሰኝ
ጸሐዩ እኮ ነው ያሳበደኝ
በዘመነ ወያኔ ፍትህ ያስከጀለኝ።

## ስሚ አጣንሳ

ፈጣሪ ነኝ ካለ
ያውም የሁሉ አባት
ከሀሊ ነኝ ካለ
ሁሌም ልበ ሰፊ
አዋቂ ነኝ ካለ
አልፋ አይቀር እሜጋን
አምላክ በሉኝ ካለ
በእምሳያው ፈጣሪ
ካርታው ጠፋበት ወይ
ወይ ላይነቃ ተኛ
እውቀቱ ጠፋበት
ወይ ጉልበቱ ሳሳ?

አምላክ ነኝ ካለማ የሁሉ ሰው አበው
ዓይኑን ከፍቶ ማየት ለምንስ አቃተው?
ምነዋ አልሰማ አለ ሀገር ሙሉ ለቅሶ
የት ደረሰ ይባል ሰይጣን በዓለም ነግሶ?

ወይስ እግዜር ሰው ነው
ሁሉን ይሰለቻል
ሲሻውም ይረሳል
በሌላውም ሥቃይ ውስጥ ውስጡን ይስቃል።
አምላክ ነኝ ካለማ ሁሉንም ፈጣሪ

ሁሉንም አዋቂ
ከየትስ ደረሰ ወየት ተደበቀ
የሕዝቡንስ ጸሎት ከየት አደረሰ ?
ወዴት ወረወረ??

ሰይጣን ሲነግስብን
ካድሬ ጳጳስ ሲሆን
አማኙ ሲመተር ገዳሙ ሲለኮስ





ምነዋ ዝም አለ
ከየትስ ደረሰ
ወዴት ተደበቀ
የፈጣሪን ቦታስ ለማን አስረከበ ?

## ዛሬም እንደትላንት

የጣዖት የደም ግብር
ለጋ ወጣት ለእርድ

ሲያቀርቡ የከረሙ
የዲያብሎስን ክርፋት ዕጣን ሽቶ ብለው
ቀንዱ ጌጣችን ነው ሲሉን ሲሉ ከርመው
በደም ሰክሮ መፎዝ
ጠርሙስ ሰብሮ ጩኸት

ለዚህም አጨብጭበው
በለን ግደል እረድ
ፍጁት በለን አዘዝ
ሲሉ ጮኸው ባጅተው

ጣዖቱ ቀን ደርሶ ፍርክስ ያለ ለታ
እጥፍ ሙልጭ አሉ

ጸረ-ጣዖት አርማን ድንገት አነገቡ
ገድለው ለጣሉትም የአዞ እንባ አነቡ።

ገዳይ ተቆርቋሪ
ኢሡፓ ዴሞክራት
ወያኔም ሕዝባዊ
ሌላም ሌላም ሆነው
የፈረደበትን መምተርን ቀጠሉ
በቃላት በጥይት
ዛሬም እንደትላንት
ኢሕአፓን ገደሉ።

## ያልነበረማ

ያላየማ ያልነበረ
ጥይቱ ሲጮህ ሲንጣጣ
ልብ ፈትለክ ሊል ሲቃጣ
ቦምብ አዳፍኔው ሲፈነዳ
ያልነበረማ
የማታ ጉዞ ውጣ ውረዱን
ቁስለኛ ሸክም ርሀብ ጥሜቱን
ተቀላቀልን ከቶ ያልሰማ
በጥይት ቀርቶ በሾህ ያልደማ
በገማ ዋሻ ሥጋትን አቅፎ እንቅልፍ ያላጣ
ማደንዘዣ አልባ ቁስሉ ያልተሰፋ
ያልነበረማ ከቶ ያላየ
ከመቅጽበቱ
ከሚወደው ጋር ለዘለዓለሙ ያልተለያየ
ጓዴ ያለውም ሲከዳ ያላየ
ያልነበረማ ሁሌም ወቃሽ-ተች
የነበረውን
ሥቃይ መከራ ሸክሙ የሆነውን
ትጥቁን ሳይፈታ የታገለውን::

## ታጋይ

የትግል ሀገር የመከራ
ኢትዮጵያችን ታድላ
ታጋይ ቤተመንግሥት ገባ
በየአደባባዩም ታጋይ ሞላ
አሳሪ አራጁ ታጋይ ሆነ
አግቢ ወላጁም ታጋይ ሆነ
ጳጳሱ ሳይቀር መስቀሉን ይዞ ታጋይ ተባለ
ወንጌለ ታጋይን እየሰበከ





ምድረ መናፍቅ ተጠመቀ
አዲሱ ታጋይ በረከተ
ተለጣፊውም ተቀፈቀፈ
የጥይት ጩኸት በረከተ
አሰሳ ራሱ በዛ ወለደ
አርባጉጉ አሰቦት በሽበሽ ሆነ
ጉደጓድ እስር ቤት ከመጤፍ በዛ
ትግራይ ከሌላው ጭራሽ ተለየ
ኤርትራም በዚያው ተገነጠለ
ታጋዩ ጳጳስ ሁሉን ባረከ
ወንጌለ ወያኔን በእንግሊዝ ሰበከ
ሀገርን ማጥፋት ግዳጅ ተባለ
ወያኔ ታጋይ በደም ታጠበ
ሀገር ሊያጠፋ ምሎ ቀጠለ
እዚህም ብጻይ ከወዲያም ታጋይ
ንጉሱ ታጋይ አቡኑ ታጋይ
ያ ሼኩም ታጋይ ያ ገገርም ታጋይ
የታጋይ ክስተት የሕዝቡ ሥቃይ::

## ያም አልፏል

ያም አለፈ
ዓመት ዓመትን ተክቶ
ዛሬ ያልነውም ትላንት ሆኖ
ነገን አርቆ ከአድማስ ለግቶ::
አለፈ ልካችንን አሳውቆ አሽቶ
ጀግናን ከፈሪ ውዱን ከመናኛ ለይቶ
እስኪያልፍ ማልፋቱን አረጋግጦ
የማያልፍ መስሎ ከርሞ
ለማጀት ጽድዲት
ለጴጥሮስ ይሁዳነት አጋልጦ
ሀፍረት ማቅን አከናንቦ
ወኔን ሰልቦ አዋርዶ

ለመሀይም መንጋ ሁሌ አሰግዶ
ለአረመኔ ጭራቅ በዚያው አስገብሮ
ሁሌም ስብዕናን ቀምቶ አልከስክሶ::

ያም አለፈ
የማያልፍ መስሎ ከርሞ
እምቢኝ ያሉትንም በቀይ ሽብር ፈጅቶ
አርዶ ቆርጦ ጥሎ  በገፍ ገድሎ  ቀብሮ
ወኔን ባገኘበት በጭፍን መትሮ
ፍርሀት ክህደትን ኮትኩቶ አለምልሞ
መኖር መበርከትን ለበድን አሳቅፎ
አዋርዶ
አጨማልቆ
በመቃብር ኑሮ ስንቱን በቁም ገድሎ::

ያም አለፈ
ትላንት ዛሬ ሆን
ለነገ ቦታን ለቆ
የዘላለማዊነት ፉከራው ተኖ
ተኖ ጠፍቶ
ታሪክ ሆኖ
በሕዝብ ትግል ተቸንፎ
በተስፋ ተስፈኞች ተረትቶ
ከአፈር ትቢያ ተደባልቆ::

ለፍቶ ያልተቸነፈው ተረፈ
የተልፈሰፈሰው አፈረ
በቀን ቆጠራ ኑሮ
በእንበርክት ብልጠት ተጠፍሮ
በሬሳ ክምር ላይ ተረማምዶ
ህሊናውን ገድሎ ቀብሮ
ኅርፉን አሳልፎ
የኖረው ውርደትን እንደኑሮ
አፈረ





ኢምንትነቱን በይፋ ለበሰ
በድንነቱን ታቅፎ እየቀረ ::
ያም አለፈ
የተው ዝም በል ዘመን
ገነት የተተከባበት በገሀነም
እኛ ማለቱ የሞተበት
ግለኝነት የነገሰበት
ጀግናን ማሳደድ የሰፈነበት
ፈሪ ምላሶች የተንጣጡበት
በየፈፋውም ውድ አበባዎች የረገፉበት
ሙጃ እሾሁ ለዙፋን ሥልጣን የደረሰበት
ያም ሁሉ አለፈ ትላንት ሆነ
ነገን ማስተናገድ እየተገደደ
ለእምቢኝ ባዮቹ
ለአመጽ ልጆቹ
ለሀገር ሟቾቹ
መስገዱ ግድ ሆነ ::
ዛሬም ትላንት ሆነ
ነገም ዛሬን መንታ
የዕድል ጉዳይ ሆኖ እየደጋገመ
አልፎ ሄደ ሲባል እየተመለሰ
ጊዜ ያለፋውም እየተደቆሰ
የእምቢኝ የአመጽ ጎራም
ዛሬም እንደትላንት እየተመተረ
በነፍስ ቸርቻሪዎች እየተጠበሰ
አለፈ የተባለው ላያልፍ እየማለ
ስም ቅየራ ብቻ ሥቃዩ ቀጠለ ::
የእምቢኝ አመጽ ጎራም ጭራሽ እጁን ላይሰጥ
ሁሉ ጨልምበት ላይሰግድ ለባለነፍጥ
ሕይወቱን ላይገብር ለአንገት ሰብሮ ውርደት
ላይሆን ተለጣፊ
ላይሆን ተቀጣሪ
ላይሆን ሀገሩን ሻጭ
ለባዕድ አጎብዳጅ
አለሁ አለሁ ይላል

ጭቃው እንዳይውጠው
የውርደት ወረርሽኝ ገዝቶ እንዳይጥለው
ቆርጦ ይታገላል።
ነገ ዛሬ እንዳይሆን
ሀገርም ትዝታ
ቆርጦ ይዋደቃል።
ያም አልፏል
ይህም ያው
አይቀርም ማለፉ
በሕዘብ መቸነፉ።
የማይሰደው ዋልካ
መረሬ ጭቃ እንኳን
በጸሐይ ይደርቃል።
የንጹሐን እንባም
ዛሬን ቢያሳልፍም
ነገ ይታበሳል
ሀዘን ሙሉ ልብም
በደስታ ይፈካል
እምቢኝ የሚል ካለ
የሚታገል ካለ
ጨቋኝ ይቸነፋል
ዛሬ ነገ ያልፋል
ከቶ ላይደገም ጭራሽኑ ይሞታል።
ጭራሹኑ ያልፋል።

## ሞቴን ሐውዜን ያርገው

አሟሟቴን አሳምርልኝ የሚለው ሀበሻ
ምስጢር ቢያውቅ ነው ክብርንም ቢሻ።
የዘንድሮ ሰው ጭራሽ የጅል ጅል
ባልሆነ ቦታ በድንገት ፍንግል።
ቦታ እንኳን ሳይመርጥ ሳይመራመር
በየሸንተሮው በየመንገድ ጻር





ይለዋል ፍንግል መሞቱ ላይቀር።
በአሶሳ አርባጉጉ
አሰቦት አረካ
አጋሮና ቋራ
ጌዴዎ ገዋኔ
ጂማ ሻሸመኔ
በሸዋ በጎንደር
በባሌ በሀረር
በአጋዴን አፋር
ፍንግል ክርትው ይላል
በገፍ እየሞተም ወዲያውን ይረሳል።
ሞቴን ሐውዜን አርገው ብሎ አይጸልይም
የት ብሞት ይበጀኝ ብሎ አይዘጋጅም።
ከክልል አንድ ውጪ ፍንግል ሙትት ይላል
በሺዎች ቢሞትም በገፍ ቢታረድም
ወዲያውን ይረሳል

በሐውዜን ይቀናል።

## አዲሱ ቀረርቶ

የማን ክልል ጠፍቶ የማን ሊለማ
የማንንስ ጤፍ ማነው ሚበላ
የማንን ውሀ ማነው ሚቀዳ
የማንን በሬ ማነው ሚቀላ
የማንን ክልል ማነው ሚገዛ
የማንን ፊደል ማነው ሚበደር
በማንስ ቋንቋ ማን ሊነጋገር
በማንስ ክልል ማን ደፍሮ ሊሰፍር።

ሁሉም ክልሉን ክልሌ ብሎ
ይኑር ይጥፋ እንጂ አይሄድም ዘሎ
የምን አብሮ መኖር የማንስ አንድነት
ጆሮስ ለምን ሰምቶ አጉል ወሬ ህብረት
ክልል ክልለን እንጠፋለን እንጂ
የአውሬ መፈንጫ እንሆናለን እንጂ

ማን ክልሌን ነክቶ የቻርተሬን ፍሬ
ለጥፋቴ እስቦ የቸረኝ ወያኔ::
ክልሌ አትጠፋም ሳታልፍ ሕይወቴ
ሻዕቢያ የስጠኝ የቸረኝ ወያኔ::

## የውሸት ሀበሻ

በፈረንጅ መንግሥት ተቀጥሮ
በዶላር የደለበ ሀበሻ አግኝቼ
በሾፌር ሲሄድ በፓጀሮ
ጤና ይስጥልኝ ብለውማ
ለገጨኝ ቃጣ
ዓይኑን አፍጦ
ጤሶ በቁጣ::
ገላምጦኝ አለፈ
በረረ
ታላቅ ትምህርት ሰጥቶኝ ነጎደ ::
ዶላር ማንነትን መሰረዝ መቻሉን
አስተምሮኝ ሄደ ::

## መች ገዶኝ

ፉቂ ቡዳ እኔ ጥላወጊ እኔ
ፈላሻ ቅማንቱ
ጉዴላና ወይጠው
አድጊ ነፍጠኛውም
ወላሞ ባርያውም
ሁሉም እኔ ሆኜ
ድንቁርናን ገላጭ





የጥቁር ዘረኛን ገበና አጋላጭ
የጥቁር ዘረኛን ገበና አጋላጭ
ገበና አፍረጥራጭ
እኔው እኔ ሆኜ
ደንቆሮ ቢሳደብ
በስድቡም ቢዋረድ
ከቶም ማንነቱ ዘረኛ ዝቅጠቱ
ለሁሉም ቢጋለጥ
እኔ ምን ገዶኝ
ብስደብ ብሰደብ
ብጠቁር ብቀላ
ያው ኢትዮጵያዊ ነኝ::

## መች ሀበሻ ድሀ

ይሉናል ሀበሻ ድሀ ነው የነጣ
ኋላቀር በሽታ-ቋት ጭራሽ ንብረት አልባ
ይሉናል ሀበሻ የርሀብ ምሳሌ ነው
እንደዝንብ የሚረግፍ አሳዛኝ ፍጡር ነው::
ይላሉ ሀበሻ ችጋራም ነው ጠኔያም
ሊያለፍለት ያልቻለ  ቁጥር አንድ ተውሳካም
ይላሉ ይባላል ብዙ አድምጠናል
ሁሉም ቅጥፈት ውሸት መሆኑን አውቀናል::
ሀቅ እውነቱ ሌላ መቼ ሀበሻ ድሀ
በቀልን አምርቶ ለሌለው ሚያበላ
ብሶትን አድሶ ለሀገር የሚያበላ
ዓይኑን ድሮ የሰካ ከራሱ በኃላ::

## አልሰማ ሳለው ሁሉ

መጣሁኝ ሲላቸው
ይሁን ይምጣ ያሉ
ተዉ ይቅር ሲባሉ
ሳይሰሙ የቀሩ
ጽልመት ደይኑ ሰፍኖ
ብርሀን የታያቸው
ምጸት እየመጣ
ተስፋ የወረራቸው
ዓይናቸው ታውሮ ጆሮአቸው ተደፍኖ
የመጣባቸውም መጣልን ተብሎ
ሀገር ጉድ ወረራት ሰው በቁሙ ሞቶ::

በቀናት በወራት በቅጽበት እመርታ
ሁሉም ተጋለጠ
ባንዲራም ጨርቅ ሆነ
መብትም አፈር በላ
ግድያውም ደራ::
አላይ አልሰማ ሲል የከረመ ሁሉ
ልይ ልስማ ቢል ከቶ
ዛሬ ቢፍጨረጨር
ጅብ ከሄደ ጩኸት
የሚያሳዝን ነገር
የማይፈይድ ነገር::





## ለብሔርተኞች

ወያኔ ተንኮለኛ
መርዝ ረጨ ብሔርተኛ
ጅሉ ሁሉ ተመረዘ
ብሔሬ እያለ ፈዘዘ
በየብሔሩም ተደራጀ
በወያኔ መርዝ ነሆለለ::
ወያኔ ተንኮለኛ መርዝ ረጨ ክልል ተብየ
ሰው ሁሉ አበደ ክልሌ ወይ ሞት እያለ
የወያኔም መርዝ ግቡን መታ
ብሔሬ አስብሎ ጠቢያን አስረሳ
ሰውን አጥብቦ እያበላላ::

## ደም

ቀይ ቀለም ቀይ ነው
ሳልሳም እንደዚያው ነው
ቀይ ሴትም ሞልቷል
ወንዱም ተትረፍርፏል
የአሜሪካን ሕንድም ቀይ ሕንድ ተብሏል::
አርማም ቀይ ይሆናል ትግል በደራበት
የጀግና መሰዋት በሚዘከርበት::
አርአያ ሆኖም ቀጣይ ባፈራበት::
ጥሬ ሥጋም ቀይ ነው እንዲያው በደፈና
ደምማ ቀይ ነው የሰው ከሆነማ
የአውሬ ሰው ግን ድፍርስ ጭራሹን አተላ::
ደምማ ቀይ ነው የሰው ልጅ ከሆነ
ወኔውን በአረቄ ገድሎ ካልደበነ
ህሊናውን ሸጦ ሁሉንም ካልካደ ::
ደምማ ቀይ ነው ዴበኩሉ ኃይለኛ
በትግል ላይ ሲፈስ ሕይወት ማለምለሚያ
ሀገር መጠበቂያ::

## ሰላመ ወያኔ

እጆች ለጠመንጃ ለመብቴ ላገሬ
ብሎ መነሳቱ ጠረኝነት ሆኖ
ጸረ ሰላምነት በሚልም ተወግዞ
ባዶ እጄን ብሰለፍ
መብቴ ብዬ ብጮህ
ለአንድነት ብቆም
በሰላም ለሰላም ልታገል ብሞክር
ጦርነት ሰሪዎች
　　　　　የእልቂት ፋብሪካዎች
ጣቶች ቃታ ይሳቡ ብለው አዘዙብኝ
ሬሳ ከምረው
ከአርባጉጉ ጎንደር
ከጌዴዎ ወተር
ባዲሳባ ጭምር
በኮሌጅ በመስጊድ
ሬሳ ከምረው
ንጹሐንን ገድለው
ሰላመ ወያኔን በገቢር አስረዱኝ
ጦረኛ ነህ ብለው ጦሩን ሰደዱብኝ፡፡

## ለአድርባዮቹ

የመጥምቁ አንገት ሲቀላ
　　　　　ሳሎሜ እሱ
ኢየሱስ ሲጋለጥ ሲያዝ
　　　　　ይሁዳ እሱ
ጻሐይ ስትጠፋ
　　　　　ጨለማው እሱ
ገዳይ ሲያጓራ
　　　　　ፎካሪው እሱ
ሬሳ ዙራያ ዘፈኑ ሲቀልጥ





　　　　　ክራር መቺ እሱ
የጠቃሚ ጣት ባለቤት እሱ
ዘመንም አልፎ አዲስ ሲመጣ
ትላንትን ክዶ ለዛሬ አዳሪ
ሁልጊዜም እሱ፡፡
ወኔ የከዳው እሪ ባለበት
　　　　　ያው ጯኺ እሱ፡፡
ነፍጥ ባየበት ሚጎነበሰው
ክህደት ሲደራ አለሁ የሚለው
ጀግና ሲፈለግ እልም የሚለው
ሁልጊዜም እሱ፡፡
ባንዳ ሲጠራ
ቡከን ሲፈለግ አለሁ የሚለው
ሰው ባልዋለበት በሚከረፋው
በግሞች አምባ ቤቱን የሰራው
ሁልጊዜም እሱ፡፡

## ፎረም ሰማንያ አራት

ክህደት ውሀ ፈሳሽ ተልፈስፋሽ
ፎርም የለው የራሱ
　　　　　ካልሆነ እንዲያው መልፈስፈስ
የዘመኑ ግን ፎርም ከጀለ
ቁጥር ተሰጥቶት ፎረም ተባለ
“ር“ ጠጥራ በ “ረ “ ተገታ
መድረክነቱ አጉል ጨዋታ
ቅጥረኛነቱ የሌለው ፋይዳ
ፎረም 84 ከቶ ፎርም አልባ
የክህደት ምስል የወያኔ አምባ፡፡

## ከሀገር በላይ

ለሚስት ሚስት ለባል ባል ይተካል
የወላጅ ሞትም ቢሆን በጊዜ ይረሳል
ሲባል ከርሞ
ሀገር ብትሞት ተኪ የላት
ሲባል ባጅቶ
ይሀን ሁሉ አምኖ የዱሮ ሰው
ያልታደለ ሆኖ አዲስ ክስተት አመለጠው
ሀገር ወገን ከተካደ
ለባዕድ ለሆድ ከታደረ
ግለኝነት ከነገሰ
መካለልም ከተወደሰ
ጳጳስ ሼኩም ከረከሰ
ታሪክ ራሱ ከተወገዘ
ገንጣይ ዙፋን ከወረሰ
ከሀገር በላይ ነፋስ አለ
ምቾት አለ
በቁም መሞት ገምቶ መኖር
ሚሉት ፊሊጥ አለ ::

## ምን እንበላቸው?

ምን እንበላቸው ለአዲሶቹ ሁሉ
ታሪክን ሀገርን እንረከብ ላሉ
እንበል መንግሥቱ ነው የሀገር መለያ
ወይስ መለስ ነው የሚሆን አርአያ?
ኢትዮጵያዊ ሲባል ጀግና ነው አርበኛ
ሀሰት ነው ሀቅ ነው ይነገረን ለእኛ
ብለው ቢጠይቁን
ምን መልስ እንሰጣቸው
ምን እንበላቸው?





እንበል ወይ እዩ የወያኔን መንጋ
ከርሳሙን ፈርጣጩን
ወይስ እንበላቸው ጀግና ሞልቷል ገና
ለሀገር ለወገን ቆርጦ የሚሰዋ?
ምነው ሆዳም በዛ የእኔ እኔ ባይ መንጋ
ወኔ ህሊና አልባ
ብለው ቢጠይቁ ምን መልስ እንሰጣቸው
ምን እንበላቸው?
እንበላቸው ወኔ በደርጉ ተገድሏል
ጀግናው አርበኛውም ካለቀ ጊዜ አልፏል?
ወይስ እንበላቸው ዛሬም ጀግና ሞልቷል
ጠ ዋት ባይሆን እንኳን ማታ ላይ ያምጻል?
አሊያስ እንበላቸው
ኢትዮጵያ ኢትዮጵያ ናት ታሪኳም አልዋሸ
የከርሳሙ መንጋ መች ብዙህን ሆነ ?
ወኔስ መቼ ሞቶ መቼ ተቀበረ ?
የጀግኖቹስ ትግል ከቶ መቼ ቆመ?
መለሰ ዜናዊስ ፍርሀቱን መች ጣለ
የሀገራችን ሕዝብስ ሐራሬ መች ሸሸ
የከሀዲስ መንጋ መቼ ሕዝብ ተባለ?

## ከተቻለማ ይረሳ

መርሳትን አለመርሳት ከተቻለ
ማስታወስን ጭራሽ መርሳት
ከተቻለማ ሁሉም ይረሳ
ግፉ መከራው
ክምር ሰቆቃው
ክህደት ጥቆማው
በየመንገዱ ወዳቂ ሬሳው
ቀይ ሽብሩ ነጻ እርምጃው
በእነወያኔም ሕይወቱን ያጣው
ከተቻለማ ሁሉም ይረሳ

የእነእርገጤ የእነቀልቤሳ
የእነተሾመ የእነአሊሙሳ
የእነመንግሥቱ የዚያ ሰው በላ
ሰደድ አራጁ
ሽብሩ ቀዩ
ሁሉም ይረሳ::
ማስታወስ ጭራሽ ካልጠቀመማ
ለምን ማለቱ እንዴት ማለቱ ካልፈየደማ
እነዚያ ሁሉ ወንዶቹ ጀግኖች
እነዚያ ሁሉ ሴቶቹ ጀግኖች
ከተቻለማ ሁሉም ይረሱ
ለሀገር ለወገን ሕይወት በሰጡ
ፋሺስት ጠባብን በተጋፈጡ
ሕዝብን ሚያኮራ ታሪክ በጻፉ
ከተቻለማ ሁሉም ይረሱ
መድረኩ ይሰጥ ለገዳዮቹ
አጽማቸው ይውጣ በቀላጆቹ
ትላንት ይደገም በዛሬዎቹ
ከተቻለማ ሁሉም ይረሱ::
ካልጠቀመማ ከታሪክ መማር
ሁሉም ይረሱ ትውልድ አይማር::

## ምስጢሩ ገባኝ

የሚነግረኝ ጠፍቶ ተሞኝቼ
በትምህርት ዓመታት አጥፍቼ
በቃ አበቃሁ ብዬ
ዲግሪ በተርታ ተሸክሜ
ተሞኝቼ
የእድገት-ብልጽግና ዋስትና
ትምህርት መስሎኝ ተታልዬ
ዛሬ ምስጢሩ ግልጥ ሆነልኝ
ለእድገት-ብልጽግና ዋስትና
ሀሊናን-ሰብዕናን ጭራሽ ገድሎ





ሀገር የለ ወገን ከሆድ በቀር ሁሉን ክዶ
ወያኔ ሆኖ መለጠፍ
ጠፍጥፉኝ ብሎ መነጠፍ
ምስጢሩ ይህ እንጂ
ትምህርትማ ምን ፈይዶ?

## ማናቸው?

ምግብ በሞላበት ጥላቻ ሚበሉ
ታሪክ ሳይረሳ
ሀቅም ሳይቀበር

ቅጥፈት የመረጡ
አብረው ያበጁትን አልሰራንም ያሉ
ማንነታቸውን ለመጤ አፈ ታሪክ
ሰርዘው የቆሙ
በሰውነታቸው ጭራሽ እምነት ያጡ
ጽንፍ ተወንጭፈው ወገንን የከዱ
ፍቅርን አስወግደው ጭላቻን ያቀፉ
ሲጋባ ሲዋለድ ዝንትዓለም ተዛምዶ
አብሮ የኖረውን

በልዩነት እሳት እየለበለቡ

በአዳም ካልሆነ ንክኪ የለህም
ባዕድ ነህ ሌላ ሰው ብለው ሚያራርቁ
ከድጡ ወደማጥ ከምጣድ ወደእሳት
ሁሌ የሚገቡ

እግር ጤና ሆኖ መዳህ ሚቀናቸው
የአሰሳ በደኖ ደም ያከረፋቸው
የታሪክን መብራት በጥላቻ አቅልተው
መለስ ሲጣላቸው አስመራን ለምነው
በስም ብቻ አንበሳ በግብር ግን ቀለው
አለን አለን ብለው እንደጤዛ ተነው
ጉልበተ-ቄጤማ ብርሀነ ዳፍንት
ሆነው የሚገኙ

ምግብ ባልጠፋበት ጥላቻን ወጥቀው

የሚቅበዘበዙ
ማናቸው እኚህ ጉዶች
ተርፎ ፍቅር አንድነት
በቂም በቀል ጠኔ መሞት የመረጡ?

## ወያኔ

ታሪክ አሳ ቢሆን
ቢርቢራው ወያኔ
መብት ዋርካን ቢመስል
ፋሱ ያው ወያኔ
ሰላም ርግብ ቢባል
እባቡ ወያኔ
ሀገር ብርሀን ብትሆን
ጨለማው ወያኔ
ዴሞክራሲን ስንዴ ብለን ብንጠራ
እንክርዳድ ወያኔ
አርበኛ ካልንማ

ባንዳው ያው ወያኔ
ስፋት ህብረት ሲባል
ጥበት ያው ወያኔ
እውቀት-ብስለት ሲባል
ድፍን-ቅል ወያኔ
ጥፋት ድቀት ካልን
ካልን አፈና እልቂት

ክልል ጎጠኝነት
በገፍ መግደል መፍጀት
ውሸት ሁሌም ቅጥፈት
ካልን ሀገር አጥፊ አበጋዝ የውርደት
ሁሉም ያው ወያኔ።





## ይሁዳ ሞኙ

የእግዜርን ልጅ ከድቶ
ሰላሳ ፍራንኮች ያገኘው ይሁዳ
ኢትዮጵያ ቢመጣ
ሀገር የሸጡትን
ግለሰብን ሳይሆን ሕዝብ የቀወሩትን

አግኝቶ ቢያወያይ
ምን ይሰማው ይሆን?

ክህደትን ይክዳል
ወይስ ተሞኝቼ
በሰላሳ ብቻ ኢየሱስን ሸጬ
ብሎ ይጸጸታል?
ወይስ ስም ቀይሮ
ለገሰ ይባላል?
የይሁዳ ክህደት ይገርመን ነበረ
መለስን ካየንስ በነበረ ቀረ
ይሁዳ ያሳዝናል በርካሽ የሸጠ
አንድን ብቻ ክዶ ራሱን ሰቀለ
አላየ መለስን የክህደትን ቁንጮ
ሕዝብ የሚሸጠውን ሀገርን ቸብችቦ።

## የማን ሰላም?

እንኳን የሬት ምሬት
የምናውቀው ቀርቶ
ሊመረን ይችላል ማርም ተርፎ በዝቶ
እንኳንስ ጦርነት ለዓመታት የኖርነው
ሊመረን ይችላል የወያኔ ሰላም
ጥፋት ሆኖ ያለው።

ሰላምን ማን ጠልቶ ሰላም ከተገኘ
ለእኛ ሬት የሆነን
ሰላም አለ የሚለን
በደም እየዋኘ ::

ጦርነትም ቢሆን ፍትሀዊነት አለው
ሰላምን ለማግኘት
ሀገርን ለማዳን
ሲሆን ሚካሄደው::

የጦረኛ ሰላም
የሰላምም ጦር ነው
ለሰላም ጦርነት
ጦረኝነት ሳይሆን
የዜጋ ግዳጅ ነው::

## ሴት ነኝ

ሴት ነኝ ቀሚስ ለባሽ
ለወገን አዛኝ ለሀገር አልቃሽ
ባልቴቷ እኔ እናትም እኔ
ሚስት እህት ሲባልም ምጠራው እኔ
ሴት ነኝ እኔ ለስላሳ
ለሀገሬ ጠላት ከቶ ማልሳሳ::
ሴት ነኝ እኔ የፍቅር ቋት
ልበሰፊ እሙ ጽናት::
ሴት ነኝ እኔ ቁምጣ ለባሽ
በየጦር ሜዳው ወራሪ አሳዳጅ::
ጣይቱ ነኝ ቆንጂት በሉኝ
ጽጌም እኔ መዓዛም ነኝ
በሉ እሌኒ በሉ አያልነሽ
በሉ ገነት ፋጡማ ነች
መሰረት ነቢሳ አልማዝና ዳሮ





ፈትለ ሀረገወይን አየለችም ብሎ
ስንቱ እናት ቢጠራ ስማቸው ያው የእኔ
እናት እህት ጓዲት ምንጪ ለሀገር ወኔ::
በሉ የጀግና ትርጉም ሴቲቷ እሳ ነች
ወተት ለጋሽ እናት ያገር ዋርዲያ ነች::
ሴት ነኝ እኔ የኢትዮጵያ
ባንዳን አርካሽ ባለሙያ
ሴት ነኝ እኔ ቀሚስ ለባሽ
የኢትዮጵያን እንባ አባሽ::

## ግጥም አቅቶኝ

ገጣሚ ሞልቶ
እንደአሸን በዝቶ
ብራና-ወረቀት ሁሉ ተጨርሶ
ስንት ስንኝ ጋር ገጥሞ ተበራክቶ
ዓይኔ አይቶ
ግጥም ምንድነው ብዬ ብጠይቅም
ልንገርህ ላስረዳህ የሚለኝ ሰው በዛ
ቀላል ጥያቄዬም አምባጋሮ አስነሳ::
ቃል በቃል በፊደል ሁሉ ተሸንሽና
የባቤሎች ግምብ ብቅ አለ ነፍስ ዘርቶ
የመግጠም ትርጉምም ከባድ ሆኖ ቀረ
ገጣሚ እንዲህ በዝቶ መግጠሙ ተሳነ ::

## የማይቻል እንዳይቻል

መቻልን ነው አለመቻል
አሸቀንጥሮ መጣል
ሽንፈትን ነው ማቻነፍ
በአፍጢም መድፋት
ጨለምተኝነትን ነው ማደባየት
በብሩህ ተስፋ ብርሀን ማትነን

ፍርሀትን ነው መፍራት
በጀግንነት መተካት
ራስ መድፋትን ነው መድፋት
ቀና ቀና በማለት

ውርደትን ነው ማዋረድ
ለክብር ሲሉ በመሰዋት
ገንጣይን ነው መገንጠል
በዘረኝነት ባለመበከል
መቻልን ነው አለመቻል
የማይቻል እንዳይቻል
አመጽ አምቢኝ እንዳይጠፋ
መቻልን ነው አለመቻል
አሸቀንጥሮ መጣል
ባርነትን ወግድ ማለት
የማይቻል እንዳይቻል
አጉል መቻልን ነው አለመቻል::

## ጸሎቴ

እንባ ሊፈስ ሲል ጉንጭ ሲያጣ
አፍ ሊናገር ብሎ ምላስ ሲጠፋ
አንጎል ማሰብ ቃጥቶ ብሎኑ ሲፈታ
እጅ ሊጨብጥ ሲል ጣት ሲያመነታ
እግር ጉዞ አምሮት ግትር ብሎ ሲቀር
ዓይን ማየት ጠፍቶት በአጭር ሲንሸዋረር
ዝንብ የአንበሳ ጌታ
ጅብ የአህያ ሎሌ
ሀበሻም የገንጣይ
ሆነው ጉድ ጉድ ሲባል
አይቼ ሰምቼ መፈጠሬን ጠላሁ
የመኖር ትርጉሙ በቁም ሞት ሆኖብኝ
ሞቼ ሞት አገኝ ዘንድ መጸለይ ጀመርኩኝ::





## እንዴት እናስታውሰው?

በምን እናስታውሰው?
ዴሞ በማለቱ
ቁርጥ ቀን ሲመጣ
ዲሞን በማንገቡ?
በምን እናስታውሰው?
በፊውዳል ጨለማ
ክብሪት በመጫሩ
ብርሀን በሌለበት ጎህን በማየቱ?
በምን እናስታውሰው?
ለነፍጥ መጎንበሱ ብልጠት በሆነበት
ትግሉ ነው ሕይወቴ ብሎ በመሞቱ?
በምን እናስታውሰው?
ሀገሬን አትንኳት ወገኔ አይዋረድ
ጥበትም ይወገድ

ለፋሺስቶች መንጋ ማንም አይርበድበድ
ብሎ በመስበኩ?
ሰብኮ መሸሽ ሳይሆን
አሻፈረኝ ብሎ

መስዋዕት በመሆኑ?
በማን እናስታውሰው?

በተስፋዬ ይሻል ወይንስ በአስማን
በቆንጂት-ከሊፋ ወይስ በዋሲሁን
ይሁን በበላይነህ ወይስ በደረጀ
በዳሮ መሀመድ ዳንኤል ባቢሌ
በብንያም ጸሎተ ወይስ በውብሸት
በሻምብል አምሀ ወይስ በይትባረክ
በጋይም በገለብ
በማርቆስ በአምባዬ
ተካልኝ ጸጋዬ?

በምን እናስታውሰው?
እምቢ በማለቱ
ለፋሺስት ለጠባብ ባለመቸነፉ?
መከራ ቢበዛም ቃሉን በማክበሩ?
በማን እናስታውሰው?
በእኒያ መዝሙሮቹ
በውብ ጽሑፎቹ
ኡኡታ ባሉለት
እንባ በዘሩለት
መስዋዕት በሆኑለት
ታሪክ በጻፉለት?

ሁሌም እናስታውሰው
ኢትዮጵያ በማለት
እኔ እኛ በማለት
አርበኛ በማለት
በማለት ሕዝባዊ
ለመብት ተዋጻቂ
ሀገር አስከባሪ
ድፍረት አስተማሪ
የዜጋ እንባ አድራቂ
ለሀገር ዘብ ቋሚ።

()

## ዛሬ

ትላንት ዛሬን ገጥግጦ
ነገን እምቢኝ እያለ
ጸሐይ አልጠልቅ ብላ ስትገተር
ጨረቃ መውጫ አጥታ ጠፍታ ስትቀር
ኮከብ ጨለማን ፈንጥቆ
ዛፍ ከነፋስ ተጣልቶ
ጎርፍ ከበረሀ ተፈቃቅሮ





ጢስአባይ ከስሞ ደርቆ
እንባ በደም ስር ሲፈስ
ሀሞት ጣፍጦ አንጀት ሲያርስ
ዓይን ልስማ ሲል ማየትን ጠልቶ
ጆሮ እጅ ለመሆን ተንጠራርቶ
የተገላቢጦሽ መሆን ፈሊጥ ሆኖ
ጤኔ ሲያጠግብና ጥሜትም ሲያረካ
ኢምንት ምትሀቱ ሰው ነኝ ሲል ሲያሽካካ
ምድረ ተለጣፊ ሲደረግ ሹመኛ
ቅዠት ለእውነታ ሲሆነው መንቲያ
አውሬና የሰው ልጅ እያጡ መለያ
ርግብ ቁራ ሆኖ ዝንብም ከንብ ሲሻል
ሰይጣን ገዳም ገብቶ ካድሬ ሲሆን ጳጳስ
ቅዱሱ ረክሶ ወያኔ ሲነግስ
ሀበሻ ተዋርዶ ለፈረንጅ ሲሰግድ
የሚች አጽም ለገዳይ ፖለቲካ ሲያግዝ
አርበኛ እስርቤት ባንዳ ቤተንግሥት
የባዕድ ቅጥረኛው መድረኩን ሲያጣብብ
የአንድነት ጠበቃው ከርቸሌ ሲወርድ
ዴዶች ተቀፍቅፈው ሀቀኛው ሲታፈን
የታገለው ቀርቶ የከዳው ሲሸለም
ነጠኞቹ ፋፍተው ጀግኖች ሲዋከቡ
ፈሪ ጀግና ሲባል ከርሳሙ ሀገርወዳድ
ኤርትራ ለድግስ ኢትዮጵያ ከል ለባሽ
ሀቀኛው ሲሳደድ ውሸታሙ አዛዥ
የጨቋኝ ባለሚል በክብር ሲስተናገድ

ነጻ ድምጽ ታፍኖ መድረክ ለአዲስ ዘመን
ተፈንቃይ ጃልሜዳ ከህዴ ሰገነት
ለምንባይ እስር ቤት አድርባይ ለሂልተን
የሰላም ለፋፊ የጦርነት ገፊ
የመብት አባወራ አፍኖ ገራፊ
ትላንት ዛሬ ሆኖ
ነገን አንቆ ገድሎ
ጨለማ ለጸሐይ ቦታን አለቅ ብሎ

ለገሰ ለገሰን በነፍጡ ተክቶ
ኀሀም ሳይቀድ ምሎ
ጸሐይ እናዳይወጣ በክልል ታግዶ
ሀገርም በገንጣይ በይፋ ተዋርዶ
ቅዠት እውነታ ነኝ እያለ ሲፏልል
ከሀዲና ባንዳው ሀገር ወዳድ ሲጥል
ኢትዮጵያ እሪ አለች
እንባም አፈሰሰች
ልጆቼ የት ገቡ
ምነዋስ ደከሙ
ምነው ነሆለሉ
ሆኑ ሆድ አምላኩ
ሳይዋጉም ሸሹ
ስትል አማረረች።
ሚሊዮን ወልጄ
መሆን ልባል ዛሬ
ስትል አለቀሰች።





# ክፍል ሶስት

# ሀበሺኛ

## ሀበሺኛ

ላስቲክ ቤት ሆኖልን ሩዝም እንጀራ
ኢትዮጵያን አስበላን ሞተን ሞት ስንፈራ::

()

ያለፈ ያልፍና ትላንት ዛሬ ሲታይ
የዛሬ ዛሬነት ዛሬም ትላንት ቀጣይ
ከባድ ሆኖ ቀረ ነገን ማግኘት ጉዳይ::

()

በመድረክ ላይ ጩኸት ሀገርን ያመሱት
ላንቃቸው  ተዘግቶ በተግባር ነጋሪት
ስጥ ለጥ ሰፈነ ዝምታ ነገሰ
ማድረግ ቢቀር እንኳን ምላስ የት ደረሰ?

()

ወንዶቹም አለፉ ግፍን እየገፉ
ሴቶቹም እንዲሁ ወንዱን እያስናቁ
በራቁት ሰውነት እነአጅሬ ቀሩ
ውርደት የለበሱ ጨቋኝን ያቀፉ::

()

ነጭ ሊጥ በምጣድ ዳቦ አልሆንኝ ብሎ
እሳት ጨመርኩበት አንጀቴ ተቃጥሎ
ነጭ ሊጥ አረረ በገነ ከሰለ
ጨለመ ጠቆረ ዳቦ ግን አልሆነ ::





()

ሌባ ጣት ቀስረው በሀሰት የከሰሱ
ለሀቅ የቆሙትን በውሸት ያጠቁ
ሌሊቱ ሲነጋ ሁሉም ተጋለጡ
በባዕድ መዲናም አልቻሉም ሊጠፉ
የሀሳዊ መሲህ ታሪክ ሁሌ ክፉ::

()

ሥጋ ካስፈለገ ከእነሱ ይቆረጥ
አጥንት ካስፈለገ የእነሱ ይወቀጥ
ደምም ካስፈለገ የእነሱ ደም ይፍሰስ
እኛ ተመልካች ነን ከትግሉ የማንደርስ
እኝ ጠባቂ ነን ድልን  ለመቋደስ::

()

አሳማ ከጭቃ ገብቶ ይፈነድቃል
ዝንብም ከቁሻሻ ከርሱን ያስደስታል
የሰውም ከሀዲ ሀገሩን ይሸጣል
ቆሞ ሚሄድ አውሬ ከመጣ ጊዜ አልፏል

()

በበረሀ ጉዞ እግሬ ተላላጠ
ሀሊናዬም ሄዶ በወጣበት ቀረ
ክፍት ዓይኔ ተዘጋ ልቤም ድንገት ሞተ
የመተከዝ ጉዞ በየምድረበዳው ጥሎኝ እያለፈ

()

ሳሚኝ ብላትማ በጣም ሳቀችብኝ
ሳቀች ብዬ ብስቅ ስማ ለቀቀችኝ
እንደገና ብስቅ በጥፊ አጮለችኝ
ሳቅ በእንባ ሲታጀብ ፍቅርም በጥላቻ
የኑሮ ጥፍጥና የምስጢሩ መፍቻ።

()

የእስር ቤቱ ደጃፍ መቼ ተሰበረ
መትረየስ ክላሺን መቼ ተቀበረ
መች ጨለማ አበቃ ብርሀን መች መጣ
መቼ ከልብ ሳቅን መች ክፉ ቀን ጠፋ?

()

ጸሐይ ተጨራምታ ጨረቃም ተቀዳ
ኮከቦች ጨልመው መሬትም ተገምሳ
ተምች ሀገርን ወሮ ሰብሉ ሁሉ ጠፍቶ
ሳቁ አስቸገረኝ ልቤ እበደትን መርጦ።

()

ጠረጴዛ ሙሉ ምግብ ሞልቶ ተርፎ
ያ የሚርበው ሰው ከማዕዱ ቀርቦ
ያ የሚጠማው ሰው ከአባይ ዳር ቆሞ
በክረምቱ ሞቆት ግንቦት የሚበርደው
ፍቅር የያዘው ነው ወይ ሀገር ያጣ ሰው?

()





እግዜር እንቅልፍ ይዞት ሰይጣን ተጠናክሮ
የደደቢት ቁልቋል ሾኩ ተሰራጭቶ
ሥቃያችን በዛ ደርግ ወያኔን ወልዶ።

()

ራቁቴን ብሆን ሙቀትን ለግሳ
ጎርፉ በመንፈሴ ጠርምሶ እንዳይገባ
ይዛኝ የቆየችው አቅፋና ደግፋ
እሷን ለእኔ ሰጥታ እኔን እኔ አርጋ
ድፍረቴ ድፍረቷ እኔነቴ እሷ
ሀገሬ ዓለሜ እናቴ ኢትዮጵያ።

()

የባሪያ ነጋዴ የጭቁኖች ገዳይ
የሰው ሀገር ገንጣይ ግብዝ ብልህ መሳይ
ባለወንጀል ታሪክ የሞት አጋር ሲሳይ
አሜሪካ ሚባል አውሬ ነፍሰገዳይ።

()

ትኳን መሻገር ወዶ ርቃትን ሚተኛ
ውርደት ሞትን ወዳጅ የባዕድ ቅጥረኛ
ሀገሩን የሸጠ ሸክም ወዳድ ጌኛ
ለነጭ ይጸልያል ሲነሳ ሲተኛ።

()

የልጅ ልጅነቷን ለሕዝቦች ለግሳ
ያገርወገን ፍቅርን ከሁሉ አስቀድማ
ለዓመታት ታገለች በበረሀ አደገች
በእሳት ተፈትና ወርቅ ሆና ተገኘች
አንድ ነች ላሉትም ብዙ እየሆነች
ቆንጂት ጽጌ ትባል ገነትም አያልነሽ።

0

ዋሻው መውጫ አልባ ዙሪያውን ጨለማ
ጣሪያ ምድሩም ቢሆን በሽንት የከረፋ
ከገቡ አይወጡበት ድንገት ይገቡበት
ነው ወይ ተወራራሽ ነጻነት ባርነት?

0

ሥጋ ይብሰብሳል ቀኑ ካለፈበት
ጸጉር ይሸብታል ዕድሜ ከገፋበት
ዛፍም ኀብጥ ይላል ነፋስ ሲያይልበት
ሰብዕናም ይጫጫል ውርደት ካበዛበት

0

ገና ከጠዋቱ ሕይወት ስንዘራ
አድገንም ለትምህርት ገበታ ስንበቃ
መኀንበስ ኃጢያት ነው ብላን እናታችን
አመጻ ሆኖ ቀረ የእኛ ሕይወታችን።

0

በየቀኑ ማታ ብዙ ሰው ይተኛል
መለስተኛ ሞትን እንቅልፍ ብሎ ይሸኛል
ታዲያ ሞትን መፍራት ከየት የመጣ ነው
ሞትን ፈርቶ ውርደት ማጠያቂያው ምን ነው

0





በርጩማ ተቀማጭ መች ብቅልን ያወርዳል
ከትግል ሜዳ ርቆስ ፋና እንዴት ይከናል
ውርደት የለመደስ መች ክብርን ይለብሳል
ሞትን የፈራስ ሰው መች ሕይወት ያገኛል?

0

ከዚያ ከትቢያው ላይ የወንድሜ ራሳ
በቀበሌ መንገድ የዚያች እቴ ራሳ
ተራራ ብል ገደል ማገኘው ራሳ
ራሳ በራሳ የዝምታ ጩኸት
ያ ሁሉ ሲገደል አንተ ከየት ነበርክ
ዓይን ከፍቶ መኝታን ከቶ መቼ ለመድክ?

0

ሰው ሁሉ አበደ ሰማይ ዳቦ ጣለ
መንግሥት የተባለው እውነት ተናገረ
በሀሳብ መለየት ጸጋ ነው ተባለ
የድሀውም ጩኸት ዛሬ ሰሚ አገኘ
ጊዜ ተለወጠ ሕልም እውነታ ሆነ
ጉምን ይጨብጣል ዓይኑን የጨፈነ ።

0

ጦርነት አይሉ ድኩማኑ በዛ
ዓይኑ የጠፋ ሰው እጅ እግሩን ያጣ
የጦርነት ጥፋት መቸ ሰው መጉዳቱ
የጦርነትማ ያ መጥፎ ጥፋቱ
የሰውን ኀዶሉ ለይቶ ማውጣቱ።

0

መስተዋቱ ባዶ ምስልን የማያሳይ
ዓይኑ ባዶ ጉድጓድ ተራ ብይ አስመሳይ
ጎፈሬው የማገር ወኔው የተውሶ
አድነን ይሉታል በቁሙ በስብሶ::

()

ትላንት ትግሬ ገዳይ ዛሬ አማራ ገዳይ
ትላንት ኦሮሞ ገዳይ ዛሬ አፋር ገዳይ
ትላንት ሰውን ገዳይ ዛሬም ሰውን ገዳይ
ነጋ ጠባ ገዳይ ዛሬ ነገ ገዳይ
በደም መጨማለቅ
የ "እኛ" መንግሥት ጠባይ::

()

በሞቀው ጃልሜዳ ያውም በጥምቀት ቀን
በደመራው ዕለት መስቀል አደባባይ
በሰው መሀል ሆኖ ብቸኝነት ስቃይ
ለካስ ከውስጥ ነው ብቻ መሆን ጉዳይ

()

ሀቅ ሽፍታ ሆና ገብታ ምድረበዳ
ቤቴ አሳጢስ ነው ግጨው ቤቴ ብላ
ከተማውን ለአውሬ ጥላ ኮበለለች
በረሀን የፈራ አያግኘኝ አለች::

()

ለጉልበተኛማ ጠበቃው ብዙ ነው
ለባለሥልጣኑ ደጋፊው አሸን ነው
ሀቅ ገብታ ኖራ ከጎስቋሎች ጎራ
የሚሰማት አጣች ብትጮህ ብትጣራ::





()

ሰላም ነው ይሉናል መፍትሔ-መንገዱ
ይሉናል አይጠቅምም ጠመንጃ ማንሳቱ
ሰላማዊ ሆነን አቤት ብንላቸው
ለኃይለኛ ቆመው ላይቀር ማፌዛቸው::

()

ርሀብን የረሳ ጥሜት የዘነጋ
ቅማልን የረሳ ትኋንን የረሳ
ሥቃይን የረሳ ሞትን በሩቅ ያለ
ባዕድ ሀገር ሆኖ ፋኖውን ወቀሰ
ቶሎ ቶሎ ሙቱ ሳገር አብቁኝ አለ ::

()

የፈጠርነውን ቃል ከአፋችን ቀምተው
የራሳቸው አርገው ሲያወግዙን መልሰው
እኛ በደማነው በእኛ ትግል ፍሬ
በላተኛው ሌላስ ከቶ እስከመቼ?

()

በጠራ ዓይኗ እይታ ጨረሩ ለስላሳ
ትዝታን ዳሳሾች እጆችዋ ቆርፋዳ
ከንፈርዋ ሳቅ አዘል ፈገግታዋ ገዳይ
ፍቅር የልብ እንጂ መቸ የአንጎል ጉዳይ::

()

አርባ ዓመት አለፈኝ ጸጉሬም ሸበተ
ክፉ ደግ ትዝታ ልቤን አጎበጠ
ወይ እንባ ወይ ደሜ ሁሌ እየፈሰሰ
ጊዜ በእኔነቴ አሹፎ እያለፈ ::

()

አፍማ አስቾጋሪ ጭራሽ አመጸኛ
ጌታውን ረስቶ ላበላው ቤተኛ
አፍማ አዋራጅ አልፎም ሰውን አጥፊ
የተሸጠ ጌታን ድንገት አናጋሪ

()

መለስ ዜናዊ ጨመተ መንኩሶ
እንጀራ ወጥ መብላት እርግፍ አርጎ ትቶ
ክትፎና ጥሽሎም ጭራሽ በቃኝ አለ
ዊስኪንም ሳይጠጣ ጭራሽኑ ማለ
መለስ ዜናዊ በቃ መነኮሰ
የሰውሥጋና ደም ብቻ እየቀመሰ ::

()

ስሚ አገኘ ጨኸታችን
መሬት ለአራሹ መፈክራችን
እርሶአደሩ መሬት አገኘ
መሬት ታደለው ተቀበረ ::

()

በሰንበት ዕለት ተረግዤ
በሐምሌ ጨለማ ክረምት ተወልጄ
በአጼው አድጌ በደርጉ ጎልምሼ
በወያኔማ መግብጥ መጃጃት ጀምሬ
ጭራሽ አቃተኝ መሳቅ ከልቤ::

()





ሀበሻ ሆኜ ጨለማን ወደድኩ
በጸሐይ ብርሀን ማልቀስ እያፈርኩ
ሀበሻ ሆኜ ጨለማን ወደድኩ
ልብስ ብለብስም ራቁት እየሆንኩ::
ሀበሻ ሆኜ ጨለማን ወደድኩ
ሀበሻነቴን ከሰው ደበቅኩ::

()

የተረት ተረት ዘመን መጥቶብን
የጠላነውን እምላክ ልኮብን
ሳንተኛ ሕልሙ ቅዠት ሆኖብን
ሞትም እምቢ አለን ዛሬ ኮርቶብን::

()

አስርቱ ቃላት የእነመለስ መንጋ
ከኢሳይያስ ያገኙት በሳህል በረሐ
ቀላል ነው ግልጥ ነው
ጀምሮ እስኪጨርስ ገንጥል-
ገንጥል ባይ ነው::

()

አውቆ የተኛን ሰው መቀስቀሱ ከባድ
ፍርሀት ነግሶ ሲገኝ ጠፊ ሀገርወዳድ
ሕሊና ሲቀበር ሰው በቁሙ ይሞታል
ላገር ያልሆነ ሕይወት ከገለባ ይቀላል

()

ተስፋን ለመቃብር መዳረግ ተለምዶ
የጸሐይ ብርሀን ሳይሆን ጨለማ ተመርጦ
ለዓላማ መቆምም ከጅል አስፈርጆ
ይመረት ገባልን እሬት ከንብ ቀፎ::

()

ፋብሪካ አልባ ሆነው ጦርነት የሰሩ
ሐውዜን አርባጉጉን በገፍ ያመረቱ
በአራቱ ማዕዘን ፍትሕን የገደሉ
በክልል ዘልዝለው ቀበሩን በሙሉ::

()

ደካማን ማጥቃቱ ድፍረት ከተባለ
የጅግንነት ትርጉም አውሬነት ከሆነ
አንድነት ከትምክህት አልለይም ካለ
ደም ምርመራ ማጠፍ አዋቂ ካሰኘ
ሁሉም የሚጠፋ የሚድንም የለ ::

()

የነፍስ ሚዛን ክብደቷ ጠፍቶኝ
ገለባ ታክል ተራራ ግራ ገብቶኝ
የሥጋ ጉራ በጣሙን አሰልችቶኝ
የታጋይ ጳጳስ የታደለ ገለጠልኝ
ነፍስን በክልል ሚዛን መዘነልኝ::

()





ከራስ በላይ ነፋስ ሚባልን ሰርዞ
ከራስ በላይ ሌላን አስቀድሞ ወዶ
መያዝ ማሰር ሳይሆን መልቀቅ ከሰፈነ
ፍቅር ከቶ አይሞትም እየተጣበበ ::

()

ልጆቼን ላሳድግ ብዬ ስንገላታ
እምቢኝ ማለት ትቼ ስልም ደፋ ቀና
የሕይወት ጠርዝ ኑሮን ላላጣ ስባዝን
ልጆቼም ሞቱብኝ ጠባቂ አባት አጥተው
የውርደትን ኑሮ ሚኖር የሞተ ሰው::

()

ፍርሀት አልባ መሆን መች ጅግንነት ሆነ
ድንገት ሞትን መፍራት መቸ ፈሪ አሰኘ
ድፍን ድፍረት እኮ ከእብደት ይቆጠራል
ፍርሀትን ፈርቶ በድፍረት ማቸነፍ
ጅግንነት ተብሏል::

()

እንደዘመናይ እብድ ግራ ቀኙን ሰድቦ
ላያበላ ጋብዞ ላይገድል ፎክሮ
በቃኝ ከፋኝ ይላል አሜሪካ ገብቶ
በአፍ ተኩሶ ገዳይ የዘንድሮ ፋኖ::

()

ይሻልን ስንጠብቅ ይብስ እየመጣ
ጸረ-ሕዝብ ያልነውን ጸረ-ሐገር ሲተካ
ትላንት የደም ዕንባ ዛሬም ቀጣይ ጣጣ
ትኩሱ ሬሳ ደረቁን ሲያስረሳ::

()

ኃጢዓት ሲደጋገም ጽድቅ እየመሰለን
ኃጢዓት በኃጢዓት ላይ ቆንጆቶ እየታየን
ሰው ገድለን ሳንጨርስ ሀገር መግደል ጀመርን
የመለስ ኑዛዜ ወይ የሁሉም ሰቀቀን?

()

ከቀበሮ ጉድጓድ ጅብ ዋሻ መግባቱ
ከእሳት ወደ ረመጥ ደጋግሞ መውደቁ
ለምዶብን ወንጀልን በወንጀል ማጀቡ
ወያኔን ተቀበልን በሮጠ  መንግሥቱ::

()

ሁሉ ሀገር ወዶ ሁሉ ሀገር ጥሎ
ሁሉ አዋጊ ሆኖ ተዋጊ ሟች ጠፍቶ
ቃልቻው በዛና ስልቻ ያዥ ጠፍቶ
ቆራርጦ ጨረሰን እሬት አልባ ኮሶ::

()

ጥላቻን በፍቅር ገጥመን ሳንረታ
ችግር ኑሮን ችለን በሳቅ ሳንገታ
ሕይወትን ለሀገር ሳንሰጥ ሳንሰቃይ
ደግ ቀን አይመጣ ነጻነትን አናይ::

()





በመደብ መኘታ በጢስ ጎጆ ቤቴ
ከቅማል ከትኋን ሆኖ ውይይቴ
ፈረንጅ ዲግሪ ነሳኝ ማይም ነው እያለ
እሱ ባለመደብ ዶክተር እየሆነ ::

()

መልከኛ አይደለችም ጠይም አሳ መሳይ
ቅርጽ ውበቷ ብየም ልዘፍን አልቃጣኝ
እንዲያው በደፈናው ከፉንጋ መለስ ናት
እግዜር ሳይቀር ይሆን ልቤን ለእሷ የሰጣት::

()

ደምቢዶሎ እናቴ አባቴ አዲስአባ
አጎቴ ከወሎ  አያቴ ከአድዋ
ነፍሴ ኢትዮጵያ ሆነች ቅርጫ መሆን ትታ
ተጣልታ ከመለስ ከእነሌንጮ ለታ::

()

ከቶም ውለታቢስ ይቺ ሀገር ሞኝ ነች
የሚሞትላትን በመዘከር ፈንታ ዳግም
ትቀብራለች

ሲቆርጣት ከራሚን
ሥልጣን ትሰጣለች
ይቺ ሀገር ሞኝ ናት አጥፊ ትወዳለች::

()

ስብዕናን መግደል ሌላም ሕይወት ማጥፋት
ለሥልጣን ለገንዘብ መሞትማ ቀላል
ከባዱስ መሞት ነው ለሀገር ለወገን
ለብዙሀን ሲሉ እራስን መከወን::

()

ወጣት ተጃጅሎ በአጉል ቀን ተወልዶ
ጭራቁ ጨረሰው ጠዋት ማታ አርዶ
ወጣት ተሞኝቶ ላገር ልሙት ብሎ
ሀገር ጥሎ አለፈ አለሁ ለሚል ሞቶ::

()

ጡንቻ ማሳበጡ ጠንካራ ካሰኘ
የእኔ ብጤ ድሀን መግደል ካስከበረ
ይቅርብኝ መከበር ይቅር መጠንከሬ
ምኑስ ሊጠቅመኝ ነው
አውሬ እንሰሳ ሆኜ::

()

ይቅር ለእግዜር ጥሩ የአዋቂ ውሳኔ
ፍቅርን የሚያሰፍን ሚያስወግድ ጭካኔ
መማር መተው ጥሩ ለሀገር ግንባታ
ታሪክን መርሳት ግን የሕጻን ጨዋታ::

()

ዛሬ ነገ ሳለ ትላንት ላይ ቆመን
ልናየው ልናውቀው ከቶውን ቢቻለን
ትላንት ላይ ሆነን ዛሬን በደግ ቃኝተን
ዛሬን ቀይረነው የእኛን ነገ ባረግን::





()

ክር ክርን ሲጠልፍ ቀዳዳ ይደፈናል
የክር በክር ሾኬ ሹራብ ይወጣዋል
ሰው ግን ሰውን ሲጠልፍ የሰው ነገር ሆኖ
ጉደኞቹ ይሰፋል ብዙ ሬሳ አግኝቶ::

()

ያልቀበረ ያርዳ የተባለ ይመስል
ያልነበረ ያውራ የተባለ ይመስል
የእነነበርን ወሬ ሀገሪቷን ሞላት
የነበረው ሳይሆን ያልነበረው በላት::

()

ፍቅር በጀመረው በጦፈ ግለቱ
ቀጣይ ቢሆን ኖሮ እስከዕለተሞቱ
የሰው ልጅ ድህነት በወሬ በቀረ
ፍቅር ተኮሳምኖ ጥሉ ባልዳበረ ::

()

ሞኝ ሆኜ ተላላ ጭራሹን ያልነቃሁ
ጺሐይን ጨረቃን ለመስረቅ ተነሳሁ
አላዋቂ ሆኜ የኑሮን ምስጢሩን
የብርሀን ባለቤት ጨለማ መሆኑን::

()

አባይም ይባጃል ሸንፋም ወንዝ ይባጃል
ቀንም አያልፍ ሲባል በሌላ ይተካል
ደስታ ፍቅርም በርቶ ደግሞም ድርግም ይላል
እንባና መከራም እያሸ ይከርማል::

()

ምላሰኛ መሆን ጠዋት ማታ መቅጠፍ
ችሎታ ተብሎ ተቃዋሚን ማርገፍ
ተብሎ አዋቂነት ጨቋኝ ሥርዓት ማስፈን
ተባለና ብልጠት መለስ ብልህ ሆነ
ዕድሜ ለአሜሪካ ለእንኮኹን ሄንዜ ::

()

ተንበርክኮ ጸሎት ተነጥፎ ልመና
ለአምላክ ከሆነ እንጂ ለሰውማ አይሰራ
ጎንበስ ያሉለት ሰው ልመና የበዛበት
መርገጥ መቅበር እንጂ ማዘን አይመጣለት

()

ብዙ ዓመት አለፈ ግፍን ስንገፋ
ተራራው ደጀን ነው ከሰው ልብ የሰፋ
ጭካኔ ግድያ ስሩን ሰዶለታል
ግፍ አይፈሬን መሬት እንክርዳድ ሞልቶታል፡

()

ውሀ ጠንካራ ነው ድንጋይ ይበሳሳል
ጊዜም ኃይለኛ ነው ፍቅርን ያፈርሳል
ሂደታችን ክፉ የሰው ደም ጠያቂ
ትምህርት እየጨረስን ሁሌም አላዋቂ፡

()

የቀድሞ ባላባት መሬቱን ያሰፋል
ደርግም በበኩሉ ወቴ ያግብስብሳል
ወያኔም በተራው ወያኔን ይወልዳል
ሁሉም ለጥፋቱ ልቡን ግን ያጠባል፡፡

()





በመከራ ሙጫ ከጫንቃ ተጣብቆ
ክፉ ጊዜ ጠግቦ አልወርድ ብሎ ከቶ
መሬት በእንባ ታርሳ ሬሳ ሲመረት
ምለላ በርክቶ ደግ ቀን ሲፈለግ
ምሁር ሁሉ አዘዘ የሶፋ ጦርነት
ከአልጋ መገላበጥ ከወንበር መታሸት
ከተግባር ርቆ ምላስ ማገላበጥ፡፡
በትዝታ ቀለብ የማን ነፍስ ይፋፋል
ተስፋ ብቻ በልቶስ ማንስ ይጠረቃል
ራቁቱን ሆኖ ማን ደጀን ጫፍ ያድራ
ደም ያልጠጣ ሥልጣን መቸ ታይቶ ያውቃል
ፍቅር ፋፍቶ ሰፍኖ መች ጥላቻስ ጠፍቷል?

()

ተፈጥሮን ማሳመር መቅረጽ ማስተካከል
ላሊበላ ሳይቀር አስተምሮን ነበር
ተፈጥሮን ቁጥጥር ሚባል ፈሊጥ መጥቶ
በረሀብ አለቅን ደርጉ ደርቆ ነግሶ፡፡

()

በቋራ የፈሰሰው ከዚያም በመተከል
አርባጉጉ ደርሶ አረካና ወተር
የኢሳይያስ ጢሰኛ መለስ ያ ደምአደር
ሬሳ አመረተ ከደረቀው ሀገር፡፡

()

ትላንት ሞትን ደፍረን ከትግል ጎራ ከርመን
ዛሬም ተንፋሽ ሆነን የትላንት እኛን ጥለን
ሞትን መድፈር ትተን ሞትን መሞት ፈርተን
ዛሬ በቁም ደረቅን ትላንት ሰው የነበርን፡፡

()

ጉልበተኛ ዱቄት ከነፋስ ይጣላል
የጠገበ ዋርካ ምሳር ይጋብዛል
ያበደ ሀበሻማ ወያኔን ያፈቅራል
ችኩል አደንጓሬ ሳይበሉት ሆድ ያማል
የዘንድሮም ፍቅር ሳይጀምሩት ያልቃል

0

ሁሌም የምናውቀው ጦርነት ሳይደራ
ጥይት ሳይተኮስ
ሰማይ መሬታችን ሁሌ እንደለመድነው
በቦምብ ሳይታረስ
እንደ እባብ በምላስ መግደሉ ተለምዶ
ብዙ ሰው አለቀ በሹክሹክታ ሞቶ::

0

ነብር ወደፍየል ፍየል ወደቅጠል
የአራጁ ከበሬ የበሬውም ከሳር
ሆኖ ቀረ እይታ ምስቅልቅል የክልል
ይኸኛው ሊበላ ያኛው ሊገድል::

0

በሥቃይ ተወልዶ በሥቃይ ያደገ
ባበለነፍጥ ሁሉ መከራ የተጫነ
እንባላብደም በቀር ደስታን ያልዳሰሰ
የሚበላው አጥቶ ሊከፍል ያመረተ
ያገሬ ገበሬ ሳይኖር ሁሉ ሞተ ::

0





ጦርነት አልኩ እንጂ መቸ ሞትን ጠራሁ
ታገሉ አልኩ እንጂ መቸ ከትግል ገባሁ
እሷን አቀፍኩ እንጂ ልብዋን መቸ ነካሁ
ጥጋበኛ አልፈለግኩ ልጠግብ በቃጣሁ::

0

ፎክሮ ከሚሸሸ ታሪክ ከሚያበላሽ
ቃልኪዳንን ክዶ ከሚሆን ርካሽ
ነፍሱንም ከሚጥል ከሚሆን ተልከስካሽ
ይሻለን ነበረ ባልነበር በጭራሽ::

0

ጨለማ ከሌለ መቸ ኀህ ይደምቃል
ኮሶ ካልመረረ እንዴትስ ያሽራል
በእንባ ያልራሰ ነፍስ ደስታን ከየት ያውቃል
ሞትን ያልደፈረ ሕይወቱ ጣዕም ያጣል::

0

የወያኔ ኮሶ ምሬቱ ያው ኮሶ
በጣጥሶ ይገድላል ሊያሽር ሊያድን ቀርቶ
የወያኔ ፍርድም ፍትህን ገዳይ ነው
አቡኩቶ ጋጋሪው ያ የሳህሉ ሰው::

0

ጉምን የሰረቀ ጉም ሲተን ይያዛል
በግፍ የገደለም በታሪክ ይቀጣል
ሺ ዝንብ ቢሰለፍም መሶብ መክፈት አይችል
ላገሩ የማይሞት ሰው ባይወለድ ይቅር
ሁለት ሞት ሲመጣ አንዱን ግባ የማይል::

()

እኔና ጥላዬ ለሁለት ስንጠጣ

መኖር አለን ማለት የማስመሰል ጣጣ
ሕይወቴን አጅቦ ሰውነቴ ቀፎ
ጥላዬም ሸሽብኝ እኔን ተጠይፎ::

()

የጀርመን አሳማ የአሜሪካ እርያ
የእንግሊዝ ክርክሮ አውሬ የአውስትሪያ
ገንዝብ አለኝ ብሎ ሕጻናት ይደፍራል
ቀበቶ ሲፈታ ሁሉ ይነጣበታል::

()

የሰዉ ማደሪያ በማን ተወሰነ
ሰማይስ ከመሬት መቼ ተላቀቀ
ትንሽ ሰው ትልቅ ሰው በምን ይታወቃል
መለኪያው የሆነው ልቡ በማን ታይቷል?

()

ተራራ መግፋቱ ጡንቻን ይጠይቃል
ያን አለት መሸከም ጉልበት ይፈልጋል
ፊትለፊት ግፍጫው ጎጂ በሆነበት
በዘዴ ይቀጥላል ብልህ ካወቀበት
ዘመን ተለውጦ ዛሬ ሌላ ሆኖ
ድፍረት ሆነ ብልሀት ካገር ሁሉ ጠፍቶ
ቀባሪ ሰው በዛ ሁሉ በቁም ሞቶ::

()





ድሮ የተማረ ለሀገር ይጠቅማል
ያኔ የተማረ ዘመዱን ይረዳል
የዘንድሮ ትምህርት ግቡ ተለውጦ
ተምሮ ማደንቆር ሆነ አሉ ተልዕኮ::

()

ወንዙን ለክተነው ድልድይ ሰርተንለት
ተሻግርን ቀልጥፈን ለዚያም ደርሰንለት
ድልድዩ ተሰብሮ ትውልድ ሚያገናኘው
ኩራት ታሪክ ሞተ አጥቶ ሚያሻግረው::

()

አላስቀው ብዬ ጥርሴ ረገፈ
አላይብህ ብለው ዓይኔም ዕውር ሆነ
ሀቅ አልሰማ ብለው ጆሮዬ ወደቀ
ተጠቃሚ ቢያጣ ህሊናዬ ሞተ
ግለኝነት በዝቶ ልቤ ኮበለለ
ፍርሀት ባበዛበት ሐሞቴም ፈሰሰ
ዊስኪ ካቲካላው ጉብቴን ጨረሰ
ያልነበረኝ አንጎል በሌለበት ቀረ ::

()

የሩቅ ሀገር ፋኖ ሳይተኩስ ይገድላል
ተዋጊም እያለ ከትግሉ ይርቃል
ስንዴማ በማዶ ይመስላል በረዶ
ጉዱ የሚፈላው ሲታይ ጸሐይ ወጥቶ
ጉዱ የሚፈላው ሲታይ እሳት ነዶ::

()

ሰላም ነው መፍትሔው የለም በጠመንጃ
ማደራጀት ይቅደም የለም ተኩስ ያደራጅ
በሀገር እናተኩር የለም በአሜሪካ
ሁሉን እናሰባስብ የለም በዮንጎ
ሀኪሙ በዛና መናኛ ታጋዩ
አዋቂው በዛና ቋንቋው ልዩ ልዩ
ሀገሪቷ ሞተች ቆመው ሲወያዩ::

()

ዕድላችን ሆኖ ትግሉ ከሰመረ
ዕድለቢስ ሆነን ሕይወት ካልጨከነ
ነገን መኖር ችለን ህልማችን ተሳክቶ
ዝምታን ለማድመጥ ነፍሳችን ታድሎ
መኖር የሚያረካን ሕይወት ገለጭ ሆኖ::

()

ሕይወት የለውጥ ሂደት ሁሌም ተቀያሪ
ትላንት ዛሬ ቢሆን መከራን ደጋሚ
ዛሬ ዛሬ እኮ ነው ራሱን የቻለ
ትላንት ዛሬ ቢሆን ከቶ ዛሬ አይደለ ::
ግርግር ለሌባ ስደትም ለወሬ
የነበረ እምነት መች ይታያል ዛሬ
አይዞህ ባይ ቢበዛ በርታው ቢበረክት
ሁሌም ለብቻዬ ሀዘኔን ምተክዝ::

()

የሚታመን ጠፍቶ በቃሉ የሚረጋ
ጠፍቶ ለወገን ሟች ሳገር የሚዋጋ
ክፉ ዘመን መጥቶ ሰዉ ተበላሽ
የማይድን መሰለው በደም ካልቆሸሸ ::





()

ተነጋግረን አብረን ተስማምተን አቅደን
ተራራ ልንገፋ በርታ አይዞን ብለን
ደስታን ልናሰፍን ምለን ተገዝተን
ተነጋግረን አብረን ተስማምተን አቅደን
እንስራ ማለቱን ሁላችን አቃተን::

()

እወዳት ነበረ ከልቤ ከነፍሴ
አፈቅራት ነበረ አብልጬ ከራሴ
ጊዜ ክፉ ሆኖ እሷንም ቀየራት
ታቅፌኝ የነበረ ልትነካኝ ቀፈፋት::
ስወዳት የነበር ድንገት ብትጠላኝ
የፍቅር ትርጉሙ በስተርጅና ጠፋኝ::

()

ልብማ ይሮጣል ፍላጎቱን ሊያገኝ
ምኞት ፈረሰኛ የማይሉት ቆየኝ
ጊዜ የሰጠው ቅል ድንጋይን ይሰብራል
ቅል ድንጋይን ሊሰብር ጊዜን ይጠብቃል
ልብማ ህልመኛ ሁልጊዜ ይሮጣል::

()

ፍሬውን አልበላን ተረፈን መዘዙ
ቃል ኪዳኑ እያለ ህዘን ሆነ ትርፉ
ቃል እንዳይሰበር ሕይወት ምንጣፍ ሆኖ
ሙቱ እንባባለን ደጋግሞ ደጋግሞ::

()

ያ ቅዱስ ዓላማ ስንቱን ያስለፈ
ያ ግዙፍ ቤታችን ስንቱን ያስጠለለ
እንዳልነበር ሆኖ ዛሬ ተወገዘ
የጠላቱስ ይሁን የቤተኛው ባሰ ፡፡

()

ለምን ሞቱ የሚል ጥያቄ የሚያነሳ
ፈላጊ ከመጣ ውብ አበባ ሚሻ
ንገሩት ወድቆ አልቋል ያገር ጽጌረዳ
ረግፎ በመንገድ ረግፎ በፈፋ
ቀርቶ በዝቶ ያለው እሾህ አሜኬላ፡፡

()

ልጆች ማልቀስ ትተው በሳቅ ሲፈነዱ
ንጹሐን ብዙሀን በደስታ ሲሞሉ
ሀገር በፍስሐ ደምቃ ስትፋፋ
ሞት ራሱ ሞቶ ሳይቀስፍ ሳይደነፋ
የስማዕት ሕይወት ያኔ እንዲሁ አልጠፋ

()

ብዙ ሰዓት ጉዞ ዳገት ቁልቁለቱ
ቀን ተሌት ፈተና ትምህርት የማግኘቱ
የዛሬዎቹማ ዕደለኛ ሆነው
ትምህርቱ አስተማሪው ሆኖ በደጃቸው
ውጣ ውረድ ቀርቶ መከራውም ጠፍቶ
ሁሉ ቀበጠ አሉ ትምህርትም ተጠልቶ፡፡

()

ግፍ ያስችላል ሲባል ዘመኑ አለፈና





ሞት ይሻለኝ ማለት ከምላስ ጠፋና
ተጎንብሶ መጫን መወቀጥ መረገጥ
ተወዶ ታቀፈ ተመርጦ መሰንበት፡፡

()

ጥቁር ተሸንሽኖ ቄንጥ ተበጅቶለት
ጠይም ቀይ ቀይዳማ ሚል ጌጥ ተደርጎለት
ማንነቱን ክዶ ሊነጣ ከጀለ
ማንም አልነገረው የነጭ ባሪያ እንዳለ ፡፡

()

በጨለማ ዛሬ ዓይናችንን ከፍተን
ከየተሬው ጫፍ ላይ ጎህ ሲቀድ ከታየን
ንጋትን ካልፈራን ለነገም ከታገልን
የዛሬን ጨለማ ድል እናደርጋለን፡፡

()

አጋልጡ ባይ ሲሄድ አጋልጡ ባይ መጣ
ሽብር ባዩ ሲሄድ ሽብር ሌላ መጣ
ለገሰ መንግሥቱን ለገሰውም ተካ
አንድነት ቃል ሆኖ በገቢር ግንጠላ
የለውጡ ለውጥነት ምትሀት ሆንና
ዛሬ ትላንት ሆኖ በአብዛኛው እይታ
ተፈልጎ ጠፋ ነገን የሚጠራ፡፡

()

ስንቱን የገደሉ ስንቱን ሰው የፈጁ
ዛሬ ተዘክረው በክብር ሲቀበሩ
ለፍትህ ለሀገር የሞቱት ተረስተው
ዛሬም እንደትላንት በዝምታ ታልፈው

ዛሬም እንደትላንትተ ለሞት ጽዋ ታጭተው
አሳዛኝ ነው ይሄ አሳፋሪ ክስተት
የጦቢያችን ታሪክ የሀገራችን ምጸት::

()

መከፈት ሲገባው የሚዘጋ ጆሮ
መታወር ሚመርጥ ዓይን ማየት እምቢ ብሎ
ጭራሽ ድፍን አንጎል ከማሰብ ተጣልቶ
እሪ በይ ሲፈለግ ምላስ ዝምን መርጦ
እጆችን አንስቶ አለሁ ማለት ፈርቶ
መቆጠርን ፈርቶ ሰው መሆንን ትቶ
ሕይወት አለኝ ይላለ በድን ሆኖ ሞቶ::

()

ከቶ ስላቃተን ለእኛ ለእኛው መብቃት
በራሳችን መሥራት በራሳችን መኩራት
በሀገራችን መኖር ባለን ለእኛው መርካት
ለራሳችን በቅተን ለሌላውም መርዳት
የሚቻለን ሲሆን ሲሆን ስላቃተን
ለፈረንጅ ተገዛን ውርደትን ተላብሰን::

()

የተወለድንባት ያደግንባት ምድር
ክብር እሷ ለእኛ ሕይወታችን ሳይቀር
ከቶ ማትደፈር ሞተን ሳንቀበር
የእናት እናት አኩሪ ህልው ለዘለዓለም
ሌላ ሀገር የለን ከኢትዮጵያ በቀር::

()





ኢትዮጵያ ሀገራችን ሆና ባለታሪክ
ሆና የምታኮራ ምርጥ ሀገር ጥንታዊት
ዜጎችዋ ታወሩ ሊሸሽዋት ተነሱ
ለፈረንጅ ሎተሪ ክብርዋን እየሸጡ::

()

ቅል ዋንጫ ቢሰበር በሌላ ይተካል
ወርቅ እንኳን ሲጠፋ በመደብ ይጌጣል
ሀገሩን ያጣ ሰው የት-እንዴት ይኖራል
ሀገር አልባ ኑሮስ ከሞት ምን ይሻላል?

()

ከሰደዱ ርቀው ከእሳት ግርፋቱ
የኖሩ በቅንጦት መከራን ሳይቀምሱ
ተጋብተው ተዋልደው ደህና የከረሙ
ከትግሉ ከሥቃይ ከቶው ያልተዋወቁ
መከራ ያየውን ደምቶ የሞተውን
ምነው ዛሬ ተቹ
ምላሰ ጠንካሮች ህሊና አልባ ሰዎች
ከትግል የራቁ::

()

ዓመት በዓሉ ሆኖ የእነሱ ቤት ደስታ
ጠላ ጠጅ ብሩንዶው በእነሱ ቤት ብቻ
ደስታ መደብ ወደ ከፍ ማለት አፍቅሮ
ከታች ያለው ቀረ ሀዘንን ታቅፎ
እርዛት ረሀብ ዕጣ ክፍሉ ሆኖ::

()

ለገዛ ሀገሩ ሙቱልኝ የሚለው
ከትግል ርቆ ጦር የሚሰብቀው
የዘንድሮ ሀበሻ ሁሉን አበላሸው
ለጊዜ ለራሱ ጊዜን እየሰጠው፡፡

()

ውድ ዕቃ ከሆነ በሙዳይ ይያዛል
የወላጅ ቅርስ ካለም በክብር ይቀመጣል
የዘመናችን ሰው ነገሩ ግልብጥብጥ
ልቡን ያዘጋጃል
ቂም በክብር ሊያስቀምጥ፡፡

()

በጊዜ ቆጠራ ብዙ ሕይወት ያልፋል
ሐሞት አልባ ዜጋም ግፍን ይሸከማል
የመኖር ትርጉሙ ከሞት ይቆራኛል
ድሮስ ያልኖረ ሰው መቼ ቀን ይሞታል

()

የዘንድሮ ሀበሻ በጣም ተጃጃለ
የማንንት ምስጢር አልረዳው አለ
የዘንድሮ ሀበሻ ግራ የተጋባ
መንጣትን ከጅሎ መጥቆሩን የጠላ፡፡

()





ቋቋስ ቢባል ቄሱ ሁሉ ተባለሽቶ
የጠሙ ህግጋት ድንገት ተለውጦ
ዘንድሮ ወያኔ ሁዳዴን ወዶታል
የሰው ሥጋ በልቶ የእንስሳን ይጠማል፡፡

()

የእኔው ለእኔ ሳለ በቂ የሚያረካ
የጎረቤት ሆኖ የልቤ ምርቃና
የራሴን በራሴ መኖሩ ሲቻለኝ
እንደእነሱ ልኖር ልፋቱ ገደለኝ፡፡

()

አዎም አይመስለኛል ላይሆናል እንዴታ
ስጠ ሲሉት ቀሚ የዘንድሮ ቋንቋ
መሰለኝ ግድየለኝ አይሆንም ጨዋታ
ወያኔ ኢሕአዴግ አንድነት ግንጠላ
ተናገር እያሉ የምላስ ቆረጣ፡፡

()

ጠመንጃ ጠብ መንጃ ቂምን ማራመጃ
ነድቶ ነድቶ አድራሽ ከመቃብር ቦታ
ጠመንጃ በድን-እንጨት
ጭራሽ በድን ብረት
ካጣ ግደል ሚለው ነፍስ አይታይበት
ካጣ ጠብ-ነጂ ሰው መግደል አይችልበት

()

ሀሊናማ ሳለው ነፍሱ ጽዳት ሚሻ
ጸጸት ነው ፈጣኑ ከሥርየት መዳረሻ
መጸጸት መቆጨት ወንጀል ማመን ከብዶ
ሀሊናዬ ንጹህ ማለቱ ተወዶ
ሀሊናዬ ንጹህ ማለቱ ቄንጥ ሆኖ
ወንጀለኛው በዛ ገሎ መካድ ገኖ::

()

የእህል ምርቱ በዝቶ ጥጋብ ባገር ሰፍኖ
ዜጋ ሁሉ ደልቶት ሁሉ ቆዳው ቀልቶ
ሁሉ ሲታይ ጤና አምሮበት አልፎለት
ልቡ ግን ሲከፋት ጥላሸት ሰፍሮበት::

()

ጠዋት በሳቅ ነግቶ ማታም በፈገግታ
ሁልጊዜ ጨዋታ ሁልጊዜ ደስታ
ትካዜና ሀዘን ድብርት የማይነካው
መቆጣት የማያውቅ መከፋት ያልነካው
የሁሌ ደስታ ሰው በየት ተወለደ
አለ ከተባለም ኢትዮጵያዊ አይደለ ::

()

ድሮማ ድሮ ነው ዓላማ አስቀዳሚ
መራብ መጠማቱ ትግልን አጃቢ
ድሮማ ድሮ ነው ሞትን መድፈር ተራ
ለሀገር ለወገን መሰዋት ሚያኮራ
ድሮማ ድሮ ነው በደም ታጥቦ አለፈ
ዛሬ ሰውን ገላጭ ምላስ ብቻ ቀረ ::





የመዋደድ ትርጉም የፍቅር ምስጢሩ
እኔን በአንተ በአንቺ ከልብ መተካቱ
በደጉ ቀን ሳይሆን ሲመጣም ያ ክፉ
ለፍቅር መቸገፍ እሷን ማስቀደሙ
ለፍቅር መረታት እሱን ማስቀደሙ
ሁሌም ማፍቀር በነፍስ መውደድ በየልቡ
ሁሌም ማፍቀር መውደድ ልብን ሳይቀይሩ

()

ብረት ተሸክመን በብረት ታንጸን
በብረት ለብረት ጸሪ ብረት ሆነን
በብረት ተከብረን ብረትን አዋርደን
በብረት ዲሲፕሊን የላላን ወጥረን
በብረት ሞራል-ጽናት ጠጣሩን አቅልጠን
ድል የእኛ ብንለው ብረት አቸነፈን::

()

ሰማይና መሬት ከማን እጅ አደረ
አምላክ መቸ ሞተ መቼ ተቀበረ
እያለ ይዘፍናል ያወቀ የመሰለው
ምድር ከእግሩ ሲናድ ማመን እያቃተው

()

ከሚፋጁ ዓይኖችዋ ከዝምታ ሳቋ
ከከንፈርዋ ውበት ከዚያ ድምጽ ቃናዋ
ከገዳይ ቁመና ከእንቁ ወርቅ ጠባይዋ
ትንሽ የቀመሰ ሞተ አሉ በፍቅርዋ::
የሰው ሰውነቱ ከመለያው አንዱ
አምጣ ወላጇን እናቱን መውደዱ
እናቱን የጠላ ወላጁን የረሳ
ገና ሳይቀበር ገሀነም የገባ::

በግፍ የገደለ በገፍ የመተረ
በንጹሐንም ደም ራሱን ያጠበ
ዛሬም ይከረፋል ነገም ይጠየቃል
ፍትህ ካላገኘ የሰው ደም ይጮሃል::

0

ታሪኩን የረሳ ቅርሱን የዘነጋ
የሞተለትንም ያልሰጠ ምስጋና
ጠላት ይገዛዋል ባሪያ አርጎ ቀጥቅጦ
ማን ሊያዝንለት ይሆን እሱ ራሱን ጥሎ

0





ከራስ ጋር ጨዋታ የዘንድሮ በሽታ
ሰሚ ሁሉ ጠፍቶ ተንቆ ሀበሺኛ
ለራሱ ተናግሮ ለራሱ ይመልሳል
አያዳምጥ ብሎም ራሱን ይወቅሳል::
ያገር ጆሮ ሁሉ በጋራ ተደፍኖ
መናገር ፋይዳቢስ ቃልን ማርከስ ከቶ::

ላሰቲክ ቤት ሆኖልን ሩዝም እንጀራ
ሀገር ልትጠፋ ነው ሞተን ሞት ስንፈራ
::

,,,,,,,,,,,,ተፈጸመ ,,,,,,,,,,

# ሀበሺኛ



ግጥሞች

## ሀማ ቱማ

